# ምዕራፍ 6፡ የዓላማ ህግ

## 6.1 ግልጽ ዓላማዎችን ማዘጋጀት እና ከመንፈሳዊ ዓላማህ ጋር ማስማማት

**መግቢያ**

ግልጽ ዓላማዎችን ማዘጋጀት ጉልበትዎን እንዲያተኩሩ በማድረግ ፍላጎቶችዎን እውን ማድረግ የሚያስችልዎ ልምምድ ነው። አላማዎችህን ከመንፈሳዊ ዓላማህ ጋር ስታስተካክል ወደ ጥልቅ የሆነ የህይወት ትርጉም እና ውስጣዊ መሟላት ትገባለህ። በዚህ ክፍል ግልጽ የሆኑ አላማዎችን የማዘጋጀት አስፈላጊነትን እና እንዴት ከመንፈሳዊ ዓላማችን ጋር ማስተካከል እንደምንችል እንመረምራለን።

### 6.1.1 የመንፈስህን ዓላማ ማጤን

በመንፈሳዊ ዓላማህ ላይ በማሰላሰል እና በማጤን በዚህ ምድር ላይ የተፈጠርክበትን ምክንያት መርምር። ደስታን የሚሰጦዎትን ነገር፣ ምን እንደሚወዱ እና ምን አይነት እሴቶች ለእርስዎ አስፈላጊ እንደሆኑ ለራስዎ ጊዜ በመስጠት ማጤን ይጀምሩ። በውስጥዎ በያዙት ልዩ ስጦታዎች እና ተሰጥኦዎች ላይ ያስቡ። መንፈሳዊ ዓላማዎ መረዳትዎ ከእውነተኛ ማንነትዎ ጋር የሚጣጣሙ እና አብረው የሚሄዱ አላማዎችን ለማዘጋጀት መሰረትን ይሰጣል።

### 6.1.2 በፍላጎቶችዎ ላይ ግልጽ ይሁኑ

በህይወትዎ ውስጥ በተለያዩ ዘርፎች ማለትም በግንኙነቶች፣ በሙያ፣ በጤና፣ በመንፈሳዊ እና በግል እድገት ዙርያ ከውስጥዎ ምን እንደሚፈልጉ ለመዘርዘር እና ግልጽ መስል በአዕምሮዎ ለመፍጠር ጊዜ ይውሰዱ። ከፍላጎቶችዎ ጋር የተዛመዱ ምስሎች በዓይነ ሕሊናዎ በመመልከት እና የተያያዙ ስሜቶች እንዲሰማዎት ይፍቀዱ። ከመንፈሳዊ ዓላማዎ ጋር የሚጣጣሙ አላማችንን ለማዘጋጀት ግልጽነት አስፈላጊ ነው።

### 6.1.3 አላማህን እና ሃሳብህን በወረቀት ማስፈር

አላማህን መፃፍ እነሱን ለማጠናከር፣ ትኩረትን ለመሰብሰብ፣ ተነሳሽነትን ለመፍጠር፣ እና ወደ ቁሳዊ አለም ለማምጣት ወሳኝ መንገድ ነው። አዎንታዊ ማረጋገጫዎችን ተጠቀም እንዲሁም አላማህን ስትገልጽ እንደሆነ አድርገህ ለራስህ አቅርብ። ማረጋገጫዎቹ የተወሰኑ፣ አጭር እና አዎንታዊ ይሁኑ። ለምሳሌ "ከውስጥ መሟላት እፈልጋለሁ" ከማለት ይልቅ "በውስጣዊ ፀጋ የተሞላሁ ነኝ" ይበሉ። አላማህን መፃፍ ትኩረትህን ግልጽ ወደሆነ አቅጣጫ ለመምራት እና ግልጽ መልእክት ወደ መንፈሳዊ አለም ለመላክ ይረዳናል።

### 6.1.4 ዓላማዎችን ከእሴቶች እና ከእምነቶች ጋር ማስተካከል

ዓላማዎችዎ ከእርስዎ እሴቶች እና እምነቶች ጋር የሚጣጣሙ መሆናቸውን ያረጋግጡ። አላማዎ እውነተኛ ካልሆኑ፣ ውስጣዊ እሴቶችዎ ጋር ተቃራኒ እና የሚቃወሙ ከሆኑ ውስጣዊ ግጭት ሊፈጥር እና የመፍጠር ሂደታችንን ሊያደናቅፍ ይችላል። አላማዎችህ ከእውነተኛው ማንነትህ ጋር የሚስማሙ መሆናቸውን በማረጋገጥ ከአንተ እሴቶች እና እምነቶች ጋር የማይስማሙ ከሆኑ አስፈላጊ ማስተካከያ እና እርምጃ ውሰድ።

### 6.1.5 ምኞቶችን ከውስጣዊ ስሜት እና ከአይነ ህሊና ምልከታ ጋር ማዋሀድ

የአላማህን ኃይል ለማጠንከር በጠንካራ አዎንታዊ ስሜቶች ውስጥህን መሙላት እና አላማህ ቀድሞ እንደተገለጠ ወይም እውን እንደሆነ አድርገህ በዓይነ ሕሊናህ መመልከት ተገቢ ነው። አላማዎ ሲሳካ ሊፈጠሩ የሚችሉ ውስጣዊ ስሜቶችን ማለትም ደስታን፣ ምስጋናን እና እርካታን አሁኑኑ እንደሆነ አድርገው በውስጥዎ እንዲሰማዎት ይፍቀዱ። የአይነ ህሊና ምስላዊ ምልከታ እና አስቀድመን ነገሮች እውን ሳይሆኑ ስሜቶች በውስጣችን እንዲፈጠሩ ማድረግ በእርስዎ እና በፍላጎቶችዎ መካከል የንዝረት መመሳሰል እንዲፈጠር እና ወደ ራሳችንን ተመሳሳይ ነገር እንድንስብ ያደርገናል።

### 6.1.6 የተጣጣመ እርምጃ መውሰድ

ግልጽ ዓላማዎችን ማዘጋጀት በቂ አይደለም። ከፍላጎቶችዎ ጋር አብረው የሚሄድ እና የሚጣጣሙ እርምጃዎችን መውሰድ አለብዎት። መውሰድ ያለብዎትን እርምጃዎች በመለየት የድርጊት መርሃ ግብር ይፍጠሩ። የምትወስዳቸው እያንዳንዱ እርምጃ ከአላማህ እና ከመንፈሳዊ ዓላማህ ጋር የሚስማማ መሆን አለበት። እርምጃ መውሰድ ከመንፈሳዊ ዓለም ጋር አብሮ ለመፍጠር ያለዎትን ቁርጠኝነት እና ፈቃደኝነት ያሳያል።

### 6.1.7 ሂደቱን ማመን

መንፈሳዊ አለም ለእርስዎ እየሰራ እንደሆነ እና አላማዎችዎ እና ፍላጎትዎ እየተሰሙ እንደሆነ ይመኑ። ማናቸውንም ውስጣዊ ጥርጣሬዎች ወይም ፍርሃቶች በመልቀቅ የሚፈልጉት ነገር ወደ ራስዎ እየመጣ እንደሆነ እምነት ይኑርዎት። ሂደቱን ማመናችን የመቆጣጠር ፍላጎታችንን እንድንተው እና ከመንፈሳዊ አላማችን ጋር የሚጣጣሙ የገሀዱ አለም መገለጫዎችን ለመቀበል በክፍት አዕምሮ እንድንጠባበቅ ያስችለናል።

**ማጠቃለያ**

ግልጽ አላማዎችን ማዘጋጀት እና ከመንፈሳዊ አላማችን ጋር ማስማማት ትርጉም ያለው እና የተሟላ ህይወት ለመፍጠር ሀይል የሚሰጥህ ታላቅ ለውጥ የሚያመጣ ልምምድ ነው። መንፈሳዊ አላማህን በማጤን፣ ፍላጎቶችህን ግልፅ በማድረግ፣ ሀሳቦችህን እና አላማዎችህን በመፃፍ፣ ከእሴቶችህ እና ከእምነቶችህ ጋር በማጣጣም፣ የስኬት ስሜቶችን በውስጥህ በመፍጠር እና አስቀድመን ስኬትን በመመልከት፣ እርምጃ በመውሰድ እና በሂደቱ እምነት በመያዝ ምኞቶችዎን ወደ እውነታ መቀየር የሚያስችል ታላቅ ተፅዕኖ የሚኖረው የንዝረት ጉልበት በዙርያዎ ይፈጥራሉ። ያስታውሱ ዓላማዎችን ማዘጋጀት ቀጣይነት ያለው ልምምድ ሲሆን በጊዜ ለውጥ የእርስዎ ዓላማዎችም እንዲሁ ሊሻሻሉ ይችላሉ። ከመንፈሳዊ አላማህ ጋር እንደተገናኘህ በመቆየት አላማህን ከእውነተኛው ማንነትህ ጋር ማስማማትህን ቀጥል።

## 6.2 የትርጉም እና የአቅጣጫ ስሜትን ማዳበር

### መግቢያ

በህይወታችሁ ውስጥ የትርጉም እና የአቅጣጫ ስሜትን ማዳበር የተሟላ እና አላማ ያለው ህይወት ለመኖር አስፈላጊ ነው። ግልጽ የሆነ የዓላማ ስሜት ሲኖርዎት መነሳሳት፣ መነቃቃት እና ከእውነተኛ ማንነትዎ ጋር ሰላማዊ የሆነ የመስማማት ስሜት መፍጠር ይችላሉ። በዚህ ክፍል ውስጥ በህይወታችሁ ውስጥ የትርጉም እና የአቅጣጫ ስሜትን የማዳበር አስፈላጊነትን በመመርመር እንዴት ይህን ማድረግ እንደምንችል የሚረዳ መመሪያ እናገኛለን።

### 6.2.1 በእሴትዎ እና በፍላጎቶችዎ ላይ ያሰላስሉ

በእርስዎ እሴቶች እና ፍላጎቶች ላይ በማሰላሰል ይጀምሩ። ለእርስዎ ከእውነት አስፈላጊ የሆነው ምንድን ነው? በውስጣችሁ የደስታ እና የእርካታ ስሜት የሚቀሰቅሱት የትኞቹ ተግባራት፣ እንቅስቃሴዎች ወይም መንስኤዎች ናቸው? እሴቶቻችሁን እና ምኞቶቻችሁን መለየት እና ማወቃችሁ ህይወታችሁን ለራሳችሁ አስፈላጊ ከሆኑ ነገሮች ጋር ለማስማማት እና የዓላማ ስሜት ለመፍጠር እና ለማዳበር ያግዝዎታል።

### 6.2.2 ትርጉም ያላቸው ግቦችን ማውጣት

ትርጉም ያላቸው ግቦችን ማውጣት በህይወት ውስጥ የአቅጣጫ ስሜትን ለማዳበር ቁልፍ መንገድ ነው። በሞያ፣ በግንኙነት፣ በጤና፣ በግል እድገት እና በህብረተሰብ አስተዋፅዖ እና በመሳሰሉት የህይወትዎ ዘርፎች ምን ማሳካት እንደሚፈልጉ ግምት ውስጥ ያስገቡ። ከእሴቶቻችሁ እና ከፍላጎቶቻችሁ ጋር የሚጣጣሙ ግቦችን በማዘጋጀት ዓላማ ወዳለው ህይወት እንዲመሩ ይፍቀዱ።

### 6.2.3 ምክንያትዎን ያግኙ

የእርስዎን "ለምን" መረዳት ትርጉም እና አቅጣጫን ለማዳበር ወሳኝ ነው። ለምን አንዳንድ ግቦችን ማሳካት እንደሚፈልጉ ወይም በተወሰኑ ተግባራት ውስጥ መሳተፍ እንደሚፈልጉ እራስዎን ይጠይቁ። ከድርጊትዎ በስተጀርባ ያለው ጥልቅ ምክንያት ምንድነው? የእርስዎን "ለምን" ማወቅዎ የትርጉም ስሜት በመስጠት ግቦችዎን እውን ለማድረግ እንደ ተቀጣጣይ ሀይል ይሆኖታል።

### 6.2.4 አዳዲስ ልምዶችን ማሰስ

አዳዲስ ልምዶችን በመድፈር ማሰስ ደስታን እና እርካታን የሚሰጥዎትን ተግባራት ለመለየት እና ለማወቅ ይረዳዎታል። ከምቾት ቀጠናዎ በመውጣት አዳዲስ እንቅስቃሴዎችን፣ የትርፍ ጊዜ ማሳለፊያዎችን ወይም ወደ አዲስ ቦታዎች ይጓዙ። እራስዎን ለአዲስ ተሞክሮዎች በማጋለጥ የተደበቁ ፍላጎቶችን ሊገልጡ ወይም ባሎት ነገር አዲስ እይታን ወይም ምልከታን ሊያገኙ ይችላሉ።

### 6.2.5 የግል እድገትን መቀበል

የግል እድገት በህይወትዎ ውስጥ ትርጉም እና አቅጣጫን የማዳበር ዋና አካል ነው። እራስን ማጤን፣ ራስን ማሻሻል እና እራስን ማግኘትን በሚያበረታቱ እንቅስቃሴዎች ውስጥ ይሳተፉ። ይህ መጽሃፎችን ማንበብ፣ ወርክሾፖችን ወይም ሴሚናሮችን መከታተል፣ ቴራፒን፣ ስልጠና መውሰድ፣ ወይም የማስተዋል ችሎታን እና ተመስጦን መለማድን ሊያካትት ይችላል። የግል እድገትን መቀበል ለለውጥ ዝግጁ እንዲሆኑ እና ከእውነተኛ ማንነትዎ ጋር እንዲጣጣሙ ያስችልዎታል።

### 6.2.6 ሌሎችን ማገልገል

ለሌሎች ደህንነት አስተዋጽዖ ማድረግ ለህይወትዎ ጥልቅ ትርጉም እና ዓላማ ያመጣል። ማህበረሰብዎን ለማገልገል ወይም ደግነት በተሞላባቸው ድርጊቶች ውስጥ ለመሳተፍ መንገዶችን ይፈልጉ። ይህ በፈቃደኝነት፣ በማማከር ወይም በቀላሉ ለተቸገሩት ድጋፍ በመስጠት ሊከነወን ይችላል። ሌሎችን በማገልገል የእነሱን ህይወት ብቻ ሳይሆን የራስዎን ህይወትም ያበለጽጋል።

### 6.2.7 ምስጋናን መለማመድ

የትርጉም እና የአቅጣጫ ስሜትን ማዳበር በህይወትዎ ውስጥ ያሉትን በረከቶች ማድነቅ እና መቀበልን ያካትታል። ምስጋና የምታቀርቡለትን ነገር በማሰላሰል በየቀኑ ምስጋናን መስጠትን ተለማመዱ። ይህ ልምምድ ትኩረትዎን ከጎደለው የህይወት ክፍል ይልቅ ወደ ፀጋ እና በረከት በመለወጥ የደስታ እና የእርካታ ስሜትን ይጨምራል።



### 6.2.8 ውስጣዊ ስሜትን ማመን

ውስጣዊ ስሜትዎ በህይወትዎ ውስጥ ትርጉም እና አቅጣጫን ለማዳበር ቁልፍ መመሪያ ነው። ውስጣዊ ጥበብዎን፣ ግንዛቤዎን ወይም ስሜትዎን በማመን የሚሰጣቸውን ስውር መልሶች እና መመሪያዎችን ያዳምጡ። ውስጣዊ ግንዛቤዎ ከእውነተኛው ማንነትዎ ጋር የሚጣጣሙ ውሳኔዎችን እንዲያደርጉ፣ አላማ ያለው እና የተሟላ ህይወት እንዲመሩ ይረዳዎታል።

**ማጠቃለያ**

በህይወትዎ ውስጥ የትርጉም እና አቅጣጫን ስሜት ማዳበር ዓላማ ያለው እና የተሟላ ህይወት እንዲኖርዎት የሚያስችል የለውጥ ጉዞ ነው። በእሴቶችዎ እና በፍላጎቶችዎ ላይ በማሰላሰል፣ ትርጉም ያላቸው ግቦችን በማውጣት፣ የእራስዎን ምክንያት በማግኘት፣ አዳዲስ ልምዶችን በማሰስ፣ የግል እድገትን በመቀበል፣ ሌሎችን በማገልገል፣ ምስጋናን በመለማመድ እና በውስጣዊ ስሜትዎ በመተማመን ከእውነተኛ ማንነትዎ ጋር የሚስማማ ህይወት መፍጠር ይችላሉ።

ትርጉምን እና አቅጣጫን ማዳበር ቀጣይነት ያለው ሂደት ሲሆን ሲያድጉ እና ሲቀይሩ ሊሻሻል ይችላል። ከእሴቶችዎ እና ከፍላጎቶችዎ ጋር እንደተገናኙ በመቆየት ወደ ህይወትዎ ደስታ እና እርካታን ከሚያመጣላችሁ ነገር ጋር እራስዎ ማስማማትዎን ይቀጥሉ።



## 6.3 ከከፍተኛ ዓላማዎ ጋር ያለዎትን ግንኙነት ለማጠናከር የሚረዱ ዘዴዎች

### መግቢያ

ከከፍተኛ አላማህ ጋር ያለህን ግንኙነት ማጠናከር ከእውነተኛ ማንነትህ ጋር የተስተካከለ ህይወት እንድትኖር የሚያስችል የለውጥ ጉዞ ነው። ከፍ ካለው አላማህ ጋር ስትገናኝ ጥልቅ የሆነ የመሟላት እና የትርጉም ስሜት ታገኛለህ። በዚህ ክፍል ውስጥ ከከፍተኛ ዓላማዎ ጋር ያለዎትን ግንኙነት ለማጠናከር የሚረዱዎትን ቴክኒኮችን እንመረምራለን።

### 6.3.1 ተመስጦ እና ማስተዋል

የተመስጦ እና የማስተዋል ልምምዶች ከከፍተኛ ዓላማዎ ጋር ለመገናኘት ቁልፍ መሳሪያዎች ናቸው። አእምሮዎን ለማረጋጋት፣ በትንፋሽዎ ላይ ለማተኮር እና በአሁኑ አፍታ የመገኘት ስሜትን ለማዳበር በየቀኑ የተወሰነ ጊዜ ይመድቡ። በተመስጦ ልምምድ ውስጣዊ ጥበብ እና የመመርያ አቅጣጫ ማግኘት እንችላለን። የማስተዋል ልምምዶች በአሁን ጊዜ እንዲኖሩ እና ከአሁኑ ጊዜ ጋር እንዲጣጣሙ የሚያግዝዎት ሲሆን ይህም እርምጃዎችዎን ከከፍተኛ ዓላማዎ ጋር አብረው እንዲያስኬዱ ያስችልዎታል።

### 6.3.2 ጆርናል መፃፍ እና ራስን ማጤን

ጆርናል የማድረግ እና እራስዎን የማጤን ልምምዶች ሃሳቦችዎን፣ ስሜቶችዎን እና ፍላጎቶችዎን ለመዳሰስ እድል ይሰጣሉ። ስለ ህልሞችዎ፣ ምኞቶችዎ እና ልምዶችዎ ለመመዝገብ መደበኛ ጊዜን ይመድቡ። በእሴቶችዎ፣ በፍላጎቶችዎ፣ እንዲሁም ደስታን እና እርካታን በሚያመጡልዎ ነገሮች ላይ ያሰላስሉ። ጆርናል ማድረግ ስለ ከፍተኛ አላማዎ ግልጽነት እና ግንዛቤን እንድታገኙ የሚፈቅድ ሲሆን ግንኙነትዎን የሚገቱ ውስን እምነቶች ወይም ቅጦችን እንዲለዩ ያግዝዎታል።

### 6.3.3 መነሳሻን እና መመሪያን ከሌሎች መፈለግ

ከከፍተኛ ዓላማቸው ጋር ከተጣመሩ ሌሎች ግለሰቦች መነሳሻን እና መመሪያን መፈለግ በሚያስደንቅ ሁኔታ ጠቃሚ ሊሆን ይችላል። መጽሐፎችን ያንብቡ፣ ፖድካስቶችን ያዳምጡ፣ ወይም ከግል እድገት እና መንፈሳዊ ዓላማችን ጋር የተያያዙ ርዕሶችን የሚዳስሱ ወርክሾፖች እና ሴሚናሮች ውስጥ ይሳተፉ። በጉዞዎ ላይ እርስዎን ሊደግፉዎት እና ሊያበረታቱዎት ከሚችሉ ተመሳሳይ አስተሳሰብ ካላቸው ግለሰቦች ጋር እራስዎን ይከበቡ።

### 6.3.4 ከተፈጥሮ ጋር መገናኘት

ተፈጥሮ እኛን መሰረት የማስያዝ እና ከራሳችን ከሚበልጥ ነገር ጋር የምታገናኝበት ልዩ እና ድንቅ መንገድ አላት። በፓርክ ውስጥ በእግር መጓዝ፣ በተራሮች ላይ የእግር ጉዞ ማድረግ፣ ወይም በቀላሉ ውሀ ባለበት ስፍራ በመቀመጥ በተፈጥሮ ውስጥ ጊዜ ያሳልፉ። በተፈጥሮ ውስጥ ጊዜ በማሳለፍ እና የፍጥረት ዓለምን ውበት እና ትስስር በመመልከት ከከፍተኛ ዓላማዎ ጋር ያለዎትን ግንኙነት እንዲያስታውስዎት ይፍቀዱ።

### 6.3.5 ውስጣዊ ግንዛቤን እና መመሪያ መቀበል

ከከፍተኛ ዓላማዎ ጋር ያለዎትን ግንኙነት ለማጠናከር ውስጣዊ ግንዛቤዎን ማዳበር እና የውስጥ መመሪያዎን ማመንን መለማመድ አስፈላጊ ነው። በውስጣችሁ ለሚነሱ ስውር መልዕክቶች፣ የሆድ ስሜቶች እና ገላጭ ግንዛቤዎች ትኩረት ይስጡ። ከምክንያታዊ አስተሳሰብዎ ጋር የሚቃረን ቢሆንም እንኳን ውስጣችሁን ማዳመጥ እና መከተልን ተለማመዱ። ውስጣዊ መመሪያዎ ወደ ከፍተኛ አላማዎ እየመራዎት እንደሆነ ይመኑ።

### 6.3.6 እራስን መንከባከብን እና ራስን ማፍቀርን ማዳበር

ራስዎን መንከባከብ እና ማፍቀርን መለማመድ ከከፍተኛ ዓላማዎ ጋር ያለዎትን ግንኙነት ለማጠናከር ወሳኝ ነው። እንደ የአካል ብቃት እንቅስቃሴ፣ ጤናማ አመጋገብ፣ እረፍት ያለው እንቅልፍ እና ደስታን በሚሰጡዎት እንቅስቃሴዎች ላይ በመሳተፍ የአካል፣ የስሜት እና አእምሮአዊ ደህንነትዎን ያሳድጉ። ከከፍተኛ ዓላማዎ ጋር የተጣጣመ ህይወት ለመኖር ብቁ መሆንዎን በማወቅ እራስዎን በደግነት እና በርህራሄ ይያዙ።

### 6.3.7 ተደጋግመው የሚገለጡ ክስተቶችን እና ምልክቶችን መቀበል እና ማቀፍ

በህይወትዎ ውስጥ ተደጋግመው ለሚታዩ እና ለሚከሰቱ ተመሳሳይ ክስተቶች እና ምልክቶች ትኩረት ይስጡ። እነዚህ አጋጣሚዎች ከከፍተኛ ዓላማዎ ጋር የሚጣጣሙ እና ትርጉም ያላቸው የአጋጣሚዎች፣ ምልክቶች ወይም መልዕክቶች ሊሆኑ ይችላሉ። ለእነዚህ ምልክቶች ክፍት እና ተቀባይ በመሆን ወደ እውነተኛው መንገድዎ እየመሩዎት እንደሆነ ይመኑ።

**ማጠቃለያ**

ከከፍተኛ ዓላማህ ጋር ያለህን ግንኙነት ማጠናከር ትጋትን እና ራስን መመርመርን የሚጠይቅ የለውጥ ጉዞ ነው። እንደ ተመስጦ እና ማስተዋል ያሉ ቴክኒኮችን በማካተት፣ ጆርናል በመፃፍ እና ራስን በማጤን፣ ተነሳሽነት እና መመሪያን ከሌሎች በመፈለግ፣ ከተፈጥሮ ጋር በመገናኘት፣ ውስጣዊ ግንዛቤ እና ውስጣዊ መመሪያን በመቀበል፣ እራስን መንከባከብን እና ራስን ማፍቀርን በማዳበር እና ተመሳሳይ ክስተቶችን እና ምልክቶችን በመቀበል ከከፈተኛ ዓላማዎ ጋር ያልዎትን ግንኙነት ያጠናክራሉ። ይህ ጉዞ ለእርስዎ ልዩ እንደሆነ በመረዳት ባልተጠበቁ መንገዶች ሊገለጡ እንደሚችሉ ያስታውሱ። ሂደቱን በማመን፣ ለውስጣዊ መመሪያዎ ክፍት በመሆን ከፍተኛ አላማዎ ትርጉም እና እርካታ ወዳለው ህይወት እንዲመራዎት ይፍቀዱ።

# ምዕራፍ 7፡ የምስጋና ህግ

## 7.1 ፀጋ እና ደስታን ለመሳብ የምስጋና ኃይልን መጠቀም

**መግቢያ**

ምስጋና ህይወትዎን የሚቀይር፣ ፀጋ እና ደስታን የሚያመጣ ታላቅ ተፅዕኖ ያለው ልምምድ ነው። የምስጋና አስተሳሰብን ስታዳብር ትኩረትህን ከጎደለው ነገር ወደ በህይወትህ ዋጋ ወዳለው ነገር እንድትቀይር ይረዳሀል። በዚህ ክፍል የምስጋና ኃይልን እንዲሁም እንዴት ፀጋ እና ደስታን ለመሳብ እንደሚረዳ እንመረምራለን።

### 7.1.1 ዕለታዊ የምስጋና ልምምድ ማዳበር

የእለት ተእለት የምስጋና ልምምድን በዕለት ተዕለት እንቅስቃሴዎ ውስጥ በማካተት ይጀምሩ። በህይወትዎ ውስጥ ያሉ በረከቶችን ለማድነቅ በየቀኑ ጥቂት ጊዜዎችን ይውሰዱ። ይህ በጆርናል ዝግጅት፣ የምስጋና ዝርዝር በመፍጠር ወይም በቀላሉ ምስጋናን በጸጥታ በአእምሮዎ በመግለጽ ሊከናወን ይችላል። ያለዎትን ፀጋ ያለማቋረጥ እውቅና በመስጠት እና በማድነቅ የበለጠ ፀጋ፣ በረከት እና ደስታን ወደ ህይወትዎ ይጋብዛሉ።

### 7.1.2 አሁን ባለው ቅጽበት ላይ ማተኮር

ምስጋና በአሁኑ ጊዜ በማስተዋል ሲተገበር በጣም ኃይለኛ ነው። ያለፈውን ከማሰብ ወይም ስለወደፊቱ ከመጨነቅ ይልቅ ሙሉ በሙሉ በአሁኑ አፍታ ለመገኘት እና አሁን ያለውን ፀጋ መቀበልን እራስዎን ያሰልጥኑ። በአሁኑ ጊዜ ላይ በማተኮር በዙሪያዎ ያለውን ፀጋ እና ደስታን ሙሉ በሙሉ ሊለማመዱ እና ሊያደንቁ ይችላሉ።

### 7.1.3 ትንንሽ ነገሮችን ማድነቅ

በህይወት ውስጥ ላሉ ትልልቅ ነገሮች አመስጋኝ መሆን አስፈላጊ ቢሆንም ደስታን እና እርካታን የሚያመጡልዎትን ትናንሽ ነገሮችን ችላ አይበሉ። ለምሳሌ እንደ ሞቅ ያለ የቡና ስኒ፣ የፀሃይ ጀምበር ስትጠልቅ፣ ወይም ከምትወደው ሰው ደግነት የተሞላባቸውን ቀላል ደስታዎች በማስተዋል ተመልከት። ትናንሽ ነገሮችን በማድነቅ ለዕለት ተዕለት በረከቶች የአመስጋኝነት ስሜትን ያዳብራሉ።

### 7.1.4 በአስቸጋሪ ጊዜያት ምስጋናን መለማመድ

ምስጋና ማለት በህይወት ውስጥ ላሉት መልካም ነገሮች ማመስገን ብቻ መለማመድ ሳይሆን በአስቸጋሪ ጊዜያት ፀጋን እና በረከትን መመልከት እና ማግኘትም ጭምር ነው። ችግሮች ሲያጋጥሙዎት ከልምዶቹ የሚመጡትን ትምህርቶችን፣ የእድገት እድሎችን ወይም የጥንካሬ ጊዜዎችን ይፈልጉ። አመለካከትዎን በመቀየር እና በአስቸጋሪ ሁኔታዎች ውስጥም እንኳን ምስጋናን በማግኘት ፈተና እና መሰናክሎችን ወደ ግላዊ እድገት እና ማበረታቻ መቀየር ይችላሉ።

### 7.1.5 ለሌሎች ምስጋናን ግለጽ

ለሌሎች ምስጋናን መግለጽ በህይወታችን ፀጋን እና ደስታን ለማዳበር ወሳኝ መንገድ ነው። በህይወታችሁ ውስጥ አዎንታዊ ተጽእኖ ላደረጉ ሰዎች ምስጋና ለመክጠት እና ለማድነቅ ጊዜ ይውሰዱ። ይህ ከልብ ከሚመነጩ ንግግሮች፣ በእጅ በተጻፉ ማስታወሻዎች ወይም በደግነት ተግባራት ሊከነወን ይችላል። ለሌሎች ምስጋናዎችን በመግለጽ መንፈሳቸውን ከፍ ማድረግ ብቻ ሳይሆን የራስዎን የግንኙነት ስሜት ያጠናክራሉ።

### 7.1.6 ምኞቶችዎን በአመስጋኝነት እና በአይነ ህሊናዎ መመልከት

ምኞቶችዎን እውን ለማድረግ የምስጋና ኃይልን ከአይነ ህሊና ምልከታ ጋር ያዋህዱ። ግቦችዎን እና ህልሞችዎን ቀድመው እውን እንደሆኑ አድርገው በአዕምሮዎ ለመመልከት በየቀኑ ጊዜ ይውሰዱ። እነዚያን ምኞቶች በማሳካት የሚመጣውን የምስጋና እና የደስታ ስሜት አስቀድመው ይሰማዎት። ምስጋናህን ከምኞትህ ጋር በማጣጣም እና አብሮ በማስኬድ ወደ ህይወትህ ፀጋ እና ደስታን የሚስብ ሃይለኛ የንዝረት ጉልበት በዙርያህ ትፈጥራለህ።

### 7.1.7 በደግነት ተግባራት ውስጥ መሳተፍ

በደግነት ተግባራት ውስጥ መሳተፍ ምስጋናን ለመግለጽ እና ደስታን ለማሰራጨት ዋንኛው መንገድ ነው። በትናንሽ የደግነት ተግባራትም ሆነ በትላልቅ ሌሎችን ለመርዳት እድሎችን ይፈልጉ። በምላሽ ምንም ነገር ሳንጠብቅ ለሌሎች ቁሳዊም ሆነ ቁሳዊ ያልሆኑ የደግነት ተግባራትን በመከወን በአለም ላይ የአዎንታዊነት እና የፀጋ ተፅዕኖ ይፈጥራል።



**ማጠቃለያ**

የምስጋና ኃይልን መጠቀም ወደ ህይወትዎ ፀጋን እና ደስታን ሊስብ የሚችል ለውጥ የሚያመጣ ልምምድ ነው። ዕለታዊ የምስጋና ልምምድን በማዳበር፣ በአሁኑ አፈታ በማተኮር፣ ጥቃቅን ነገሮችን በማድነቅ፣ በአስቸጋሪ ጊዜያት ምስጋናን በመለማመድ፣ ለሌሎች ምስጋና በመግለጽ፣ ምኞቶችዎን በአመስጋኝነትና በአይነ ህሊና በመመልከት እና የደግነት ተግባሮችን በመለማመድ ወደ እርስዎ የበለጠ በረከቶችን እና አዎንታዊ የህይወት ልምዶችን ይጋብዛሉ። ምስጋናን እንደ የመኖር መንገድ በመቀበል ፀጋ፣ በረከት እና ደስታ ወደ ህይወትዎ ሲፈስ ይመልከቱ።

## 7.2 አመለካከትን ለመቀየር በየቀኑ የምስጋና ልምምድን ማዳበር

### መግቢያ

እለታዊ የምስጋና ልምምድን ማዳበር የእርስዎን አመለካከት ለመቀየር እና በህይወትዎ ላይ አወንታዊ ለውጥ ለማምጣት ወሳኝ መንገድ ነው። ሆን ብለህ እና በማስተዋል ምስገና በምሰጣቸው ነገሮች ላይ ስታተኩር በዙሪያህ ያለውን ፀጋ እና በረከት መመልከትን አእምሮህን ታሠለጥነዋለህ። በዚህ ክፍል ውስጥ የእርስዎን አመለካከት ለመቀየር የሚረዱ ዕለታዊ የምስጋና ልምምድ እንዴት ማዳበር እንደምንችል እንመረምራለን።

### 7.2.1 የምስጋና ጆርናል በመፃፍ መጀመር

ምስጋና የሚገባቸውና የምሰጣቸውን ከሶስት እስከ አምስት የሚደርሱ ነገሮችን በመጻፍ ምስጋናን ለመግለፅ በየቀኑ ጥቂት ደቂቃዎችን መድብ። እነዚህ ትልቅ፣ ትንሽ፣ የተመረጠ ወይም ሁሉንም የሚያጠቃልል ሊሆኑ ይችላሉ። የመጻፍ ተግባር በህይወትዎ ውስጥ ያሉትን በረከቶች ሙሉ በሙሉ እንዲገነዘቡ እና እንዲያደንቁ ይረዳዎታል። ይህንን የእለት ተእለት ልማድ በማድረግ እይታዎ ወይም አመለካከትዎን መቀየር ይችላሉ።

### 7.2.2 የምስጋና ተመስጦን መለማመድ

በተመስጦ ልምምድዎ ውስጥ ምስጋናን ያካትቱ። ጸጥ ያለ ቦታ በመቀመጥ አይኖችዎን ይዝጉ። ከዛንም እራስዎን ወደ አሁኑ አፍታ ለመመለስ በተደጋጋሚ ትንፋሽ ይውሰዱ። በመቀጠልም ምስጋና ለሚሰጧቸው ነገሮች ሙሉ ትኩረትዎን ይስጡ። በልብዎ ውስጥ ያለውን ምስጋና ሙሉ በሙሉ እንዲሰማዎት በመፍቀድ በፀጥታ ወይም ጮክ ብለው ይግለጹ። ይህ ልምምድ ጥልቅ የሆነ የአድናቆት ስሜት በውስጥዎ እንዲፈጠር እና ትኩረትዎን ወደ አዎንታዊነት እንዲቀይሩ ይረዳዎታል።

### 7.2.3 የምስጋና ማሰሮ ማዘጋጀት

በቤትዎ ውስጥ የምስጋና ማሰሮ ያዘጋጁ። በየቀኑ ምስጋና መስጠት የምንፈልገውን ነገር በትንሽ ወረቀት ላይ በመፃፍ በማሰሮው ውስጥ ያስቀምጡ። ከጊዜ በኋላ ማሰሮው በህይወትዎ ውስጥ ባሉ የበረከት በማስታወሻዎች ይሞላል። አዎንታዊ ስሜትን በውስጥዎ መጨመር በሚፈልጉበት ጊዜ ሁሉ በማሰሮው ውስጥ ያሉትን ማስታወሻዎች ለማንበብ ትንሽ ጊዜ ይውሰዱና አመስጋኝ መሆን ያለብዎትን ዝርዝር ምክንያቶች ያስታውሱ።

### 7.2.4 ለሌሎች ምስጋናን መስጠት

ለሌሎች ምስጋናን መግለጽ መንፈሳቸውን ከፍ የሚያደርግ ብቻ ሳይሆን የእራስዎን የአመስጋኝነት ስሜት ያጎላል። በህይወትዎ ያሉትን ሰዎች ለማመስገን እና ለማድነቅ ጊዜ ይውሰዱ። አድናቆትህን ለማሳየት ማስታወሻ መፃፍ፣ በቃል መግለፅ ወይም የደግነት ተግባራትን አድርግ። ምስጋናህን በመግለፅ ወደራስህ አወንታዊ ተዘዋዋሪ ተጽእኖ ትፈጥራለህ። ይህም የፀጋ እና የበረከት አስተሳሰብን ያጠናክራል።

### 7.2.5 የምስጋና የእግር ጉዞዎችን ማድረግ

የምስጋና የእግር ጉዞዎችን በማድረግ ወደ ተፈጥሮ ምስጋና እራስዎን ይውሰዱ። ስትራመዱ በዙሪያህ ያለውን ውበት ተመልከት እንዲሁም አድንቅ። የተፈጥሮን ቀለሞች፣ ድምፆች እና ሽታዎች አስተውል። ለዛፎች፣ አበቦች፣ እንስሳት እና በዚያ ቅጽበት ለመገኘት ያገኘህውን እድል በምስጋና ተቀበል። ይህ ልምምድ ከተፈጥሯዊው አለም ፀጋ ጋር እንድትገናኝ በማድረግ አመለካከትህን ወደ ምስጋና ይለውጠዋል።

### 7.2.6 ምስላዊ የምስጋና ማስታወሻዎችን መጠቀም

ምስላዊ የምስጋና ማስታወሻዎችን በአካባቢዎ ውስጥ ያስቀምጡ። ይህ የምስጋና ሰሌዳ፣ ምስጋና የምንሰጣቸውን ነገሮች የሚወክሉ ምስሎች ወይም የምስጋና ማረጋገጫዎች ያሉት ተለጣፊ ማስታወሻ ሊሆኑ ይችላል። እነዚህ ምስላዊ ማስታወሻዎች የእርስዎን አመለካከት ለመቀየር እና በህይወትዎ አዎንታዊ ገጽታዎች ላይ እንዲያተኩሩ ለማስታወስ እንደ ማበረታቻ ያገለግላሉ።

### 7.2.7 በፈተና ጊዜያት ምስጋናን መለማመድ

በአስቸጋሪ ጊዜያት ምስጋናን መለማመድ በማንነታችንም ሆነ በህይወታችን ላይ ታላቅ ተፅዕኖ ሊኖረው ይችላል። ከፈታኝ ሁኔታዎች የሚነሱ ትምህርቶችን፣ የእድገት እድሎችን ወይም የጥንካሬ ጊዜዎችን ይመርምሩ። በችግሩ ላይ ከማተኮር ይልቅ እይታዎን ወደ ተግዳሮቶቹን በማሸነፍ ለሚመጣው ፅናት እና እድገት ምስጋናን ይስጡ። ይህ ልምምድ በአስቸጋሪ ጊዜ ውስጥም አዎንታዊ አመለካከትን ለማዳበር ይረዳል።

**ማጠቃለያ**

የእለት ተእለት የምስጋና ልምምድን ማዳበር የእኛን አመለካከት ለመቀየር እና በህይወታችን አወንታዊ ለውጥ ለማምጣት የሚያስችል የለውጥ መንገድ ነው። ከምስጋና ጆርናል በመጀመር፣ የምስጋና ተመስጦን በመለማመድ፣ የምስጋና ማሰሮ በማዘጋጀት፣ ምስጋናን ለሌሎች በማካፈል፣ በምስጋና የእግር ጉዞዎች በማድረግ፣ ምስላዊ ማስታወሻዎችን በመጠቀም እና በፈተና ጊዜያት ምስጋናን በመለማመድ አእምሮዎን በበረከቶች እና በፀጋዎች ላይ እንዲያተኩር ያሠለጥናሉ። ምስጋናን እንደ ዕለታዊ ልማድ በመቀበል የእርስዎ አመለካከት ወደ አዎንታዊነት፣ ደስታ እና ለአሁኑ ጊዜ ጥልቅ አድናቆት እና ወደ ግንዛቤ ሲሸጋገር ይመልከቱ።

## 7.3 የምስጋና ስሜት በደህንነትዎ እና በግንኙነትዎ ላይ የሚያሳድረው ተፅዕኖ

### መግቢያ

ምስጋና ለግል እድገት ወሳኝ ልምምድ ብቻ ሳይሆን በደህንነትዎ እና በግንኙነቶችዎ ላይም ከፍተኛ ተጽእኖ ይኖረዋል። በውስጣችሁ ያለውን የምስጋና ስሜት ስታሳድጉ ከራሳችሁ በላይ የሚዘልቅ እና በአካባቢያችሁ ባሉት ሰዎች ላይ በጎ ተጽዕኖ የሚያሳድር ተዘዋዋሪ ተጽእኖ ይፈጥራል። በዚህ ክፍል ውስጥ በደህንነትዎ እና በግንኙነትዎ ላይ አመስጋኝነት ያለውን ተፅእኖ እንመረምራለን።

### 7.3.1 የተሻለ የአእምሮ እና ስሜታዊ ደህንነት

ምስጋናን መለማመድ የተሻለ የአእምሮ እና የስሜታዊ ደህንነት ያስከትላል። ምስጋና በምስጣቸው ነገሮች ላይ ስታተኩር ትኩረትህን ከአሉታዊ ሀሳቦች እና ስሜቶች ወደ አዎንታዊ ስሜት ይለውጣል። ምስጋና የደስታ ስሜትን፣ እርካታን እና አጠቃላይ ደህንነትን በመጨመር ጭንቀትን፣ ጫናን እና ድብርትን ይቀንሳል። ምስጋናን በመለማመድ እና በማዳበር ለአእምሮዎ እና ለስሜታዊ ጤንነትዎ አዎንታዊ መሰረት ይጥላሉ።

### 7.3.2 የተሻለ አካላዊ ጤንነት

ምስጋና በአካላዊ ጤንነት ላይ አዎንታዊ ተጽእኖ አለው። ጥናቶች እንደሚያሳዩት አመስጋኝ ግለሰቦች እንደ መደበኛ የአካል ብቃት እንቅስቃሴ፣ የተሻለ እንቅልፍ እና ጤናማ የአመጋገብ ልማዶች ባሉ ጤናማ ባህሪያት ውስጥ የመሳተፍ አዝማሚያ አላቸው። ምስጋና የሰውነትን በሽታ የመከላከል አቅምን ይጨምራል፣ የደም ግፊትን ይቀንሳል፣ እንዲሁም ሥር የሰደደ ሕመም መንስኤዎችን ይቀንሳል። ምስጋናን በመለማመድ አጠቃላይ አካላዊ ደህንነትዎን ያጠናክራሉ።

### 7.3.3 የጠነከረ ግንኙነት

ግንኙነቶችን በመገንባት እና በማጠናከር ረገድ ምስጋና ወሳኝ ሚና ይጫወታል። ለሌሎች ምስጋና ስትገልጽ የአድናቆት ስሜት እና ግንኙነትን ያዳብራል። በተጨማሪም ምስጋና መተሳሰብን፣ ርህራሄን እና መረዳትን ስለሚያሳድግ አመስጋኝ ግለሰቦች አወንታዊ እና አርኪ ግንኙነቶች የመፍጠር እና የማዳበር እድላቸው ሰፊ ነው። ለሚወዱት ሰዎች ምስጋናን በመግለጽ ትስስርዎን ያጠናክራሉ እንዲሁም አዎንታዊ እና ደጋፊ አካባቢን ይፈጥራሉ።

### 7.3.4 የመቋቋም አቅም መጨመር

ምስጋና በችግሮች እና በፈተና ጊዜ የመቋቋም አቅምን ለመገንባት ይረዳል። ምስጋናን ስትለማመድ ትኩረትህን ከጎደለው እና ከሌለው ነገር ይልቅ ወደ አሁኑ አፍታ በመመለስ በህይወት ስላለው እና አስፈላጊ ወደሆነው ነገር እንድትቀር ያደርግሃል። ይህ የአመለካከት ለውጥ በአስቸጋሪ ጊዜም እንኳን ጥንካሬን፣ ተስፋን እና ትርጉምን እንድታገኝ ይፈቅድልሃል። ምስጋናን በማዳበር የህይወትን ውጣ ውረዶች በአዎንታዊ አስተሳሰብ ለመምራት ፅናት ያዳብራሉ።

### 7.3.5 ፀጋ እና በረከትን መሳብ

ምስጋና ፀጋ እና በረከትን ወደ ህይወታችን ለመሳብ እንደ ማግኔት የሚያገለግል ነው። አመስጋኝ በሆንበት ነገር ላይ ስናተኩር አዎንታዊ የንዝረት ጉልበት ወደ መንፈሳዊ አለም ትልካለህ ይህም ተመሳሳይ በረከቶችን እና ፀጋዎችን ወደ ህይወትህ ትስባለህ። በዙሪያህ ያለውን ፀጋ እና በረከት ባደነክ እና እውቅና በሰጠህ ቁጥር የበለጠ ነገርን ወደ ራስህ ትጠራለህ። ምስጋናን በማዳበር ከራስዎ በላይ የሚዘልቅ እና በግንኙነቶችዎ እና ልምዶችዎ ላይ በጎ ተጽእኖ የሚፈጥር የፀጋ እና የበረከት ዑደት ይፈጥራሉ።

### 7.3.6 ሌሎችን ማነሳሳት

የምስጋና ውጤት ከቅርብ ግንኙነቶችዎ በላይ ይዘልቃል። ምስጋናን ስትለማመድ በዙሪያህ ያሉትን በማነሳሳት አወንታዊ ተጽእኖ ያሳድራል። የእርስዎ ምስጋና ለሌሎች አርአያ ሆኖ ሊያገለግል፣ ተመሳሳይ የአመስጋኝነት እና የአዎንታዊ አስተሳሰብ እንዲከተሉ ያበረታታል። ምስጋናን በህይወትዎ በማካተት ሌሎች የራሳቸውን የምስጋና እና የደህንነት ስሜት እንዲያሳድጉ ለማነሳሳት ሀይል ይሰጣሉ።

### 7.3.7 አወንታዊ አካባቢ መፍጠር

ምስጋና የሚኖሩበትን እና የሚገናኙበትን አካባቢ የመለወጥ ኃይል አለው። ያለማቋረጥ ምስጋናን ስትገልጹ ግልጽ የሆነ ግንኙነትን፣ ደግነትን እና ድጋፍን የሚያበረታታ አዎንታዊ አከባቢን ይፈጥራል። በግንኙነትዎ እና በማህበረሰቦችዎ ውስጥ የምስጋና ባህልን በማዳበር ለሁሉም ይበልጥ ተስማሚ የሆነ አካባቢ እንዲኖር አስተዋፅዖ ያደርጋሉ።



**ማጠቃለያ**

የምስጋና ውጤት በጣም ሰፊ ሲሆን ደህንነትዎ እና ግንኙነቶችዎ ላይ አዎንታዊ ተፅዕኖ ያሳድራል። ምስጋናን በመለማመድ የአዕምሮ እና የስሜት ደህንነትዎን መጨመር፣ አካላዊ ጤንነትዎን ማሻሻል፣ ግንኙነቶችዎን ማጠናከር፣ የመቋቋም አቅም መጨመር፣ ፀጋ እና በረከትን ወደራስዎ መሳብ፣ ሌሎችን ማነሳሳት እና ማበረታታት፣ እንዲሁም በዙርያዎ አዎንታዊ አካባቢን መፍጠር ይችላሉ። ምስጋናን እንደ የህይወት መንገድ በመቀበል የተንሰራፋው አዎንታዊ የንዝረት ጉልበትዎ ተፅእኖ በህይወትዎ እና በዙሪያዎ ያሉ ሰዎች ህይወት ውስጥ ደስታን፣ ቀናነትን እና እርካታን ሲያሰራጭ ይመልከቱ።

# ምዕራፍ 8: ያለመጣበቅ ህግ

## 8.1 መጣበቅን መተው እና ለመንፈሳዊ አለም ፍሰት መሰጠት

**መግቢያ**

ከውጫዊ አለም መጣበቅን መተው እና ለመንፈሳዊ አለም ፍሰት መሰጠት ሰላምን፣ ነፃነትን እና ጥልቅ የህይወት ትስስርን ሊያመጣ የሚችል ታላቅ ተፅዕኖ ያለው ተግባር ነው። በዚህ ምእራፍ ውስጥ መጣበቅን ስለመተው እና ለመንፈሳዊ አለም የመሰጠትን ጽንሰ ሃሳብ እንቃኛለን።

### 8.1.1 መጣበቅን መረዳት

የመጣበቅ ፍላጎት ደህንነትን፣ ደስታን ወይም ቁጥጥርን ለማግኘት ከሰዎች፣ ነገሮች፣ ሁኔታዎች ወይም ውጤቶች ጋር ከመጠን በላይ እራሳችንን የመጣመር ዝንባሌን ያመለክታል። ከመጠን በላይ የሆነ ቁርኝት ወይም መጣበቅ ጊዜያዊ ማጽናኛ ሊሰጥ ቢችልም ብዙ ጊዜ ነገሮች እንደታቀደው ሳይሄዱ ሲቀሩ ወይም ከአቅማችን በላይ የሆኑ ሁኔታዎችን ለመቆጣጠር ስንሞክር ወደ ስቃይ ይመራናል።

የመጣበቅ ፍላጎት የሰው ልጅ ተፈጥሯዊ ዝንባሌ ቢሆንም ይህ ፍላጎት አሁን ያለንበትን ጊዜ ሙሉ በሙሉ እንዳንለማመድ እና ህይወት የምሰጠንን እድሎች ለመቀበል ያለንን አዝማሚያ ሊገድብ ይችላል።

### 8.1.2 የነገሮች ጊዜያዊነትን መቀበል

የመጣበቅ ባህሪን ለመልቀቅ እና ለመተው ቁልፍ ከሆኑ ነገሮች አንዱ የህይወትን ጊዜያዊነት መቀበል ነው። በህይወት ውስጥ ያለ ሁሉም ነገር ያለማቋረጥ በለውጥ ላይ ነው። ይህ ግንዛቤ ካለን ነገሮችን፣ ሁኔታዎችን ወይም ሰዎችን ለዘላለም አንድ አይነት ሆነው እንደሚቆዩ ማመን እና መቀበል ከእውነታ የራቀ እና የተሳሳተ አመለካከት መሆኑን እንረዳለን።

የህይወት ጊዜያዊነትን በመቀበል ለአዳዲስ ልምዶች ክፍት የመሆን እና ቶሎ የመላመድ ችሎታን ማዳበር እንችላለን። ይህም ከምንመኘው ነገር ጋር ከመጣበቅ ወይም የማንፈልገውን ከመቃወም ይልቅ በመንገዳችን የሚመጡ ለውጦችን እና ፈተናዎችን እንድንቀበል እና አብረን እንድንፈስ ያስችለናል።

### 8.1.3 አለመጣበቅን መለማመድ

አለመጣበቅን ለመለማመድ ለውጤቶች፣ ለምንጠብቀው ነገር እንዲሁም ውጪ ካለው ነገር ቀርቶ ከራሳችንን ማንነት ጋር ያለንን መጣበቅ ጭምር መተውን ይጨምራል። ለእያንዳንዱ የህይወታችንን ክፍል ያለንን የመቆጣጠር ፍላጎትን መተው እና ለተፈጥሮ የህይወት ፍሰት መገዛትን ያካትታል።

ያለፍርድ እና መጣበቅ ሃሳቦችዎን፣ ስሜቶችዎን እና ፍላጎቶችዎን ከከፍታ ሆነው መመልከትን ይለማመዱ። በአካላዊ አለም ውስጥ ያሉ በረከት እና ፀጋዎች ጊዜያዊ ልምምዶች መሆናቸውን አውቀው እንዲመጡና እንዲሄዱ ይፍቀዱላቸው። አለመጣበቅን በእለተ ተእለት በመለማመድ የውስጣዊ ሰላም እና የነጻነት ስሜትን ማዳበር እንችላለን።



### 8.1.4 መንፈሳዊ አለምን ማመን

ለመንፈሳዊ አለም ፍሰት መገዛት በእኛ ውስጣዊ ፍላጎት ላይ የሚሰራ የበለጠ ታላቅ መንፈሳዊ ሀይል እንዳለ፣ እየመራን እና እኛን እየደገፈን እንደሆነ ማመንን ያካትታል። የሕይወታችንን ሁሉንም ገፅታዎች የመቆጣጠር ፍላጎትን መተው እና ነገሮች እንደታሰቡ እንደሚሆኑ ማመን ማለት ነው።

መንፈሳዊ አለም ለእርስዎ ታላቅ እቅድ እንዳለው በማመን ምንም እንኳን ከእርስዎ የቅርብ ፍላጎቶች ወይም ምኞቶች ጋር የማይጣጣሙ ቢመስሉም ማመን አያቁሙ። ለመንፈሳዊ አለም ፍሰት መገዛት ተቃውሞን እንድንተው እና በመንገዳችን የሚመጡ እድሎችን እና ትምህርቶችን እንድንቀበል ያስችለናል።

## 8.1.5 የማስተዋል ችሎታን ማዳበር

ማስተዋል መጣበቅን ትተን ለመንፈሳዊ ዓለም ፍሰት እራሳችንን እንድንሰጥ የሚረዳን ተፅዕኖ ያለው ልምምድ ነው። የአሁኑ ጊዜ ግንዛቤን በማዳበር ሀሳቦቻችንን፣ ስሜቶቻችንን እና ልምዶቻችንን ውስጥ ሳንሰምጥ እና ሳንጠመድ እራሳችንን ሆነ አከባቢያችንን መመልከት ያስችለናል።

በተመስጦ፣ በጥልቅ በሆነ የአተነፋፈስ ዘዴ ወይም በቀላሉ ለአሁኑ ጊዜ ትኩረት በመስጠት ማስተዋልን ተለማመዱ። ይህ ልምምድ ከመጣበቅ የፍላጎት አዝማሚያ እንድንለይ እና ከራሳችን ጥልቅ መንፈሳዊ ማንነት ጋር እንድንገናኝ ይረዳናል።

**ማጠቃለያ**

መጣበቅን መተው እና ለመንፈሳዊ ዓለም ፍሰት መሰጠት ሰላምን፣ ነፃነትን፣ እርካታን፣ መረጋጋትን እና ጥልቅ የህይወት ትስስርን ሊያመጣ የሚችል የለውጥ ተግባር ነው። ይህም የሕይወትን ጊዜያዊነት በመቀበል፣ አለመጣበቅን በመለማመድ፣ መንፈሳዊ አለምን በማመን እና የማስተዋል ችሎታን በማዳበር ተፅዕኖአቸውን መቀነስ እንችላለን። መጣበቅን በመተው እና ለመንፈሳዊ ዓለም ፍሰት በመገዛት በሕይወታችን ውስጥ የላቀ የሰላም፣ የደስታ እና የእርካታ ስሜት ማግኘት እንችላለን። አስታውስ ህይወት ቀጣይነት ያላት የለውጥ ጉዞ ናት። ያለመጣበቅ መኖርን በመለማመድ እና ለፍሰቱ በመሰጠት በመንገዱ ላይ የሚገለጡ ውበቶችን እና እድሎችን መቀበል እንችላለን።

## 8.2 በመንፈሳዊ አለም ጊዜ ማመን እና ተአምራት በጊዜአቸው እንዲገለጡ መፍቀድ

### መግቢያ

የመንፈሳዊ አለምን ጊዜ ማመን እና ተአምራት በራሳቸው ጊዝ እንዲገለጡ መፍቀድ ህይወት ለምታቀርብልን እድሎች ለመሰጠት፣ እምነት ለመያዝ እና ክፍት አዕምሮ ለመያዝ የሚጋብዝ ተግባር ነው። በዚህ ክፍል ውስጥ በመንፈሳዊ ጊዜ መታመንን እና በህይወታችን ውስጥ ያሉ ተአምራትን የመቀበል ጽንሰ-ሀሳብን እንመረምራለን።

### 8.2.1 መንፈሳዊ ጊዜን መረዳት

በመንፈሳዊ ጊዜ ማመን የሕይወታችንን ክስተቶች እና ሁኔታዎች የሚመራ ታላቅ መንፈሳዊ ኃይል ወይም ፈጣሪ እንዳለ ማመንን ያመለክታል። ከግል ምኞታችን፣ ፍላጎታችን ወይም ከምንጠብቀው ነገር ጋር ባይጣጣምም ሁሉም ነገር በራሱ መንፈሳዊ ጊዜ እንደሚሆን ይጠቁማል።

ከእኛ ስጋዊ እቅድ የበለጠ መንፈሳዊ አለማ እንዳለ በመረዳት እና በማመን የሚያጋጥሙን የህይወት ክስተቶች ሁሉ የተቀነባበሩት ለበጎ እና ለእኛ መንፈሳዊ እድገት እንደሆነ ይመኑ።

### 8.2.2 ቁጥጥርን መልቀቅ

በመንፈሳዊ ጊዜ እምነት ለመጣል የቁጥጥር ፍላጎትን መተው አስፈላጊ ነው። ከአቅማችን በላይ የሆኑ የህይወት ገፅታዎች እንዳሉ መረዳት ተገቢ ሲሆን ውጤቶችን ለማስገደድ ወይም ለመቆጣጠር መሞከር ብዙ ጊዜ ወደ እርካታ እጦት እና ስቃይ ይመራል።

በምትኩ ለሂደቱ መሰጠትን እና ህይወት ትግላዊ ባልሆነ ተፈጥሮአዊ መንገድ እንድትገለጥ መፍቀድን ተለማመዱ። መንፈሳዊ አለም ለእርስዎ እቅድ እንዳለው በማመን ነገሮች በትክክለኛው መንገድ እና ጊዜ እንደሚገለጡ እና እየተገለጡ እንዳሉ እምነት ይኑርዎት።

### 8.2.3 ትዕግስትን ማዳበር

መንፈሳዊ ጊዜን ማመንን በተመለከተ ትዕግስተኛ መሆን ወሳኝ ገፀባህርይ ነው። አንዳንድ ነገሮች ከተጠበቅነው ጊዜ በላይ ሊወስዱ እንደሚችሉ ወይም እርስዎ ባሰቡት መንገድ ላይሆኑ እንደሚችሉ ይረዱ። ሂደቱን በማመን እና በመቀበል ለእራስዎ የእድገት እና ለሁኔታዎች የመገለጥ ሂደት ትዕግስት ይኑርዎት።

ትዕግስትን ማስተዋልን በመለማመድ፣ ለራስ ርህራሄ በመስጠት፣ ራስን በመረዳት እና ሁሉም ነገር በራሱ ጊዜ እንደሚከሰት እራስዎን በማስታወስ መንፈሳዊ አለም ለእርስዎ የሚበጀውን እንደሚያውቅ እና ትክክለኛ አጋጣሚዎች በትክክለኛው ጊዜ እራሳቸውን እንደሚያቀርቡ እምነት ይኑርህ።

### 8.2.4 ምስጋናን መለማመድ

ምስጋና አመለካከታችንን መቀየር የሚያስችል እና በዙሪያችን ላሉት ተአምራት እራሳችንን ለመክፈት የሚረዳን ታላቅ ተፅዕኖ ያለው ልምምድ ነው። ለአሁኑ ጊዜ እና በህይወትዎ ውስጥ ላሉ በረከቶች የምስጋና አስተሳሰብን ያሳድጉ።

አመስጋኝ በሆንክባቸው ነገሮች ላይ በማተኮር የበለጠ አዎንታዊ ልምዶችን እና ፀጋዎችን ወደ ህይወትህ ትጋብዛለህ። መንፈሳዊ አለም ሁል ጊዜ ለእኛ የጋራ ፍላጎት እንደሚሰራ በማመን እውን ለሆኑ እና ወደፊት ለሚገለጡ ተአምራት ምስጋና ስጥ።

## 8.2.5 ያልተጠበቀውን መቀበል

በመንፈሳዊ ጊዜ መተማመን ማለት ለማይጠበቁ እና ለማይገሙቱ የህይወት ክስተቶች ክፍት መሆን እና ህይወት የሚያመጣቸውን ያልታሰቡ ነገሮች መቀበል ማለት ነው። ብዙ ጊዜ ተአምራት የሚከሰቱት ብዙም ሳንጠብቀቸው እና ሳናስገድዳቸው ስንቀር ነው።

በመንገድዎ ለሚመጡ አዳዲስ እድሎች፣ ግንኙነቶች እና ልምዶች ክፍት ይሁኑ። ያልተጠበቀውን በመቀበል መንፈሳዊ አለም ለእርስዎ ያልተለመደ እና ታላቅ ነገር እንዳዘጋጀ እምነት ይኑርዎ።

**ማጠቃለያ**

በመንፈሳዊ ጊዜ መተማመን እና ተአምራት በጊዜአቸው እንዲገለጡ መፍቀድ ለህይወት ሂደት መሰጠትን፣ እምነት መያዝን እና ቁጥጥርን ለመተው ፈቃደኛ መሆንን ይጠይቃል። የህይወትዎን ክስተቶች የሚመራ መንፈሳዊ ሃይል እንዳለ በማመን ሁሉም ነገር በጊዜው እንደሚሆን ይመኑ። በሂደቱ ያሎትን እምነት ለመጨመር የቁጥጥር ፍላጎትዎን ይተዉ፣ ትዕግስተኛ ይሁኑ፣ ምስጋናን ይለማመዱ እና ያልተጠበቀውን ለመቀበል ዝግጁ ይሁኑ። በመንፈሳዊ ጊዜ በመተማመን እና ተአምራት በጊዜአቸው እንዲገለጡ በመፍቀድ እራስህን ወደ እድሎች አለም በመጋበዝ ታላቅ ደስታን፣ ብልጽግናን እና እርካታን ወደ ህይወትህ ትጋብዛለህ። አስታውስ ተአምራት የሚገለጡት ወይም እውን የሚሆኑት ሁልጊዜ ለመቀበል እምነትና ክፍት የሆነ ልቦና ካለን ነው።

## 8.3 መጣበቅን ለመልቀቅ እና አለመጣበቅን ለመቀበል የሚረዱ ዘዴዎች

### መግቢያ

መጣበቅን መልቀቅ እና አለመጣበቅን መቀበል ሰላምን፣ ነፃነትን እና ጥልቅ የህይወት ትስስርን ሊያመጣ የሚችል እና ለውጥ የሚያስከትል ተግባር ነው። በዚህ ክፍል ውስጥ መጣበቅን ለመልቀቅ እና ያለመጣበቅ ሁኔታን ለማዳበር የሚረዱዎትን የተለያዩ ዘዴዎችን እንመረምራለን።

### 8.3.1 ራስን ማጤን እና መገንዘብ

መጣበቅን ለመልቀቅ ራስን ማጤን እና መገንዘብ መቻል አስፈላጊ ናቸው። ስለ የመጣበቅ ባህሪዎ እና ስለነሱ ስር ሰደድ ምክንያቶች ለማሰላሰል፣ ለመመርመር እና ለማጤን ጊዜ ይውሰዱ። ከዛንም እንዴት ሰበቃ ወይም ስቃይ በውስጣችን እንደሚፈጠሩ እና እድገታችንን እንደሚገድቡ ልብ ይበሉ።

ያለፍርድ ስለ ሃሳቦችዎ፣ ስሜቶችዎ እና ፍላጎቶችዎ ያልዎትን ግንዛቤ ይጨምሩ። መጣበቅ በህይወትዎ ውስጥ እንዴት እንደሚገለጥ እና በደህንነትዎ ላይ ያለውን ተጽእኖ ይመልከቱ።

### 8.3.2 መጥፎ ልምዶችን መልቀቅ

መጥፎ ልምዶችን መተው የመጣበቅ ፍላጎትን ለመልቀቅ የሚረዳ ኃይለኛ መሳሪያ ሊሆን ይችላሉ። መጣበቅን ለመልቀቅ ፈቃደኛ መሆንዎን የሚያመላክቱ አዳዲስ ልምዶችን እና ሥርዓቶችን ይፍጠሩ። ይህ የመጣበቅ ባህሪያችንን በወረቀት ላይ በመጻፍ ማቃጠል ወይም መጣበቅን የሚወክሉ ነገሮችን በአካል መልቀቅን ሊያካትት ይችላል።

በእነዚህ አዲስ ልምዶች እና ሥርዓቶች ውስጥ ስትሳተፍ ንቁ ሆነህ የመጣበቅ ባህሪን ልቀቅ፣ ያለመጣበቅ መኖርን ለመቀበል እና ለህይወት ፍሰት ለመገዛት እራስህን ስጥ።

### 8.3.3 የማስተዋል ተመስጦ

የማስተዋል ተመስጦ የአሁኑን ጊዜ ግንዛቤን የሚያዳብር እና ከመጣበቅ ባህሪ ለመላቀቅ የሚረዳ ልምምድ ነው። የማስተዋል ተመስጦን ለመለማመድ በየቀኑ ጊዜ ይመድቡ።

ይህን ለማድረግ በአተነፋፈስዎ ላይ ያተኩሩ፣ በሰውነትዎ ውስጥ ያሉ ስሜቶች ያስተውሉ ወይም ልዩ ማረጋገጫዎችን ይጠቀሙ። ሀሳቦች ወይም ተያያዥ ነገሮች ሲነሱ ያለፍርድ ይመለከቷቸውና በእርጋታ የእርስዎን ትኩረት ወደ የአሁኑ ጊዜ ይመልሱ። ይህ ልምምድ በእርስዎ እና በመጣበቅ ባህሪዎ መካከል ክፍተት እንዲፈጠር በማድረግ የበለጠ መለያየት እንዲኖር ያስችላል።

### 8.3.4 አዎንታዊ ማረጋገጫዎች

አዎንታዊ ማረጋገጫዎች አስተሳሰብዎን ለመቀየር እና የመጣበቅ ባህሪን ለመልቀቅ ጠቃሚ መሳሪያዎች ሊሆኑ ይችላሉ። መጣበቅን ለመልቀቅ እና ያለመጣበቅ መኖርን ለመቀበል ፍላጎትዎን የሚያጠናክሩ አዎንታዊ ማረጋገጫዎችን ይፍጠሩ።

እነዚህን አዎንታዊ ማረጋገጫዎች በመደበኛነት፣ በጸጥታ ወይም ጮክ ብለው ይግለፁ። መጣበቅን ለመልቀቅ እና ለህይወት ፍሰት ለመሰጠት ያለዎትን ቁርጠኝነት በማጠናከር ወደ ውስጠ ህሊናዎ እንዲገቡ ይፍቀዱላቸው።

## 8.3.5 ምስጋናን ማዳበር

ምስጋና ትኩረትህን ከመጣበቅ ባህሪ ወደ አሁን ላለህ ነገር አድናቆት ለመቀየር የሚረዳ ልምምድ ነው። በህይወታችሁ ላሉት በረከቶች ለማሰላሰል እና ለማመስገን በየቀኑ ጊዜ ይውሰዱ።

በየቀኑ ምስጋና የምሰጣቸውን ሶስት ነገሮች ጻፍ ወይም ለምታምነው ሰው አካፍላቸው። ይህ ልምምድ የፀጋ እና እርካታ አስተሳሰብን ለማዳበር የሚረዳ ሲሆን የመጣበቅ ባህሪን ይቀንሳል።

**ማጠቃለያ**

መጣበቅን መልቀቅ እና ያለመጣበቅ መኖርን ማቀፍ እራስን ማጤንን፣ ማስተዋልን እና ያለንን የመጣበቅ ባህሪ ለመልቀቅ ፈቃደኛ መሆንን የሚጠይቅ የለውጥ ተግባር ነው። እራስን በማጤን እና በመገንዘብ ውስጥ ይሳተፉ፣ አዳዲስ ልምዶችን እና ስርዓቶችን ይፍጠሩ፣ የማስተዋል ተመስጦን ይለማመዱ፣ አዎንታዊ ማረጋገጫዎችን ይጠቀሙ እንዲሁም የምስጋና ልምድዎን ያዳብሩ።

እነዚህን ቴክኒኮች በዕለት ተዕለት ሕይወትዎ ውስጥ በማካተት የመጣበቅ ባህሪን ቀስ በቀስ መተው እና ያለመጣበቅ መኖርን በማቀፍ የሚገኙ ነፃነት እና ሰላምን ማግኘት ይችላሉ። አስታውስ ያለመጣበቅ መኖር ማለት በግድየለሽነት መኖር ማለት አይደለም ይልቁንም ከውጫዊ ሁኔታዎች፣ ነገሮች፣ ሰዎች እና ተመሳሳይ ነገሮች ጋር እራሳችንን በማጣበቅ ከሚመጡ ሸክሞች ለመላቀቅ ከህይወት ጋር ሙሉ በሙሉ እንዲሳተፉ የሚያስችል ክፍት እና ተቀባይነት ያለው ሁኔታ ነው።

# ምዕራፍ 9: የይቅርታ ህግ

## 9.1 የይቅርታን የመለወጥ ኃይል መረዳት

**መግቢያ**

ይቅርታ ቁስሎችን የመፈወስ፣ ስሜታዊ ሸክሞችን የማቅለል እና ውስጣዊ ሰላምን ማምጣት የሚያስችል ታላቅ ተፅዕኖ ያለው እና ለውጥ የሚያመጣ ተግባር ነው። በዚህ ክፍል ውስጥ የይቅርታን ጽንሰ ሃሳብ እና በህይወታችን ውስጥ ያለውን የለውጥ ሃይል እንቃኛለን።

### 9.1.1 ይቅርታ ምንድን ነው?

ይቅርታ ለበደሉን ግለሰቦች በውስጣችን የምንይዘውን የቂም፣ የቁጣ ስሜትን እና የበቀል ፍላጎትን መተውን ይወክላል። አፍራሽ ስሜቶችን የመልቀቅ እና ቂም ከመያዝ ሸክም እራሳችንን የምናላቅቅበት ንቁ ምርጫ ነው።

ይቅርታ ማለት የሌሎችን ድርጊት ቸል ማለት ወይም መርሳት ማለት ሳይሆን ከርህራሄ እና ከመረዳት ቦታ ሆነን ወደፊት ለመራመድ መወሰን እና ወደ ኋላ የሚጎትተንን ህመም ለመተው ፈቃደኛ መሆን ማለት ነው።

### 9.1.2 የይቅርታ ጥቅሞች

ይቅርታ ለአእምሯዊ፣ ስሜታዊ እና አካላዊ ደህንነታችን ብዙ ጥቅሞችን ይሰጣል። አንዳንድ ጥቅሞች የሚከተሉትን ያካትታሉ፦

**1. ስሜታዊ ፈውስ፦** ይቅርታ ከስሜታዊ ቁስሎች እንድንፈውስና እንደ ቁጣ፣ ቂም እና ምሬት ያሉ አሉታዊ ስሜቶችን እንድንለቅ እና እንድንተው ያስችለናል። ለብዙ ቀናት፣ ሳምንታት፣ ወሬት ወይም አመታት በውስጣችን የምንይዛቸው እነዚህ የስሜት ሸክሞች እኛን ከራሳችን የቀድሞ ሀሳብ እና ስሜት እስር በማድረግ የግል እድገታችንን የማደናቀፍ እድላቸው ቀላል የማይባል ነው።

**2. የተሻለ ግንኙነት፡-** ይቅርታ ግንኙነቶችን ለመጠገንና ለማጠናከር ይረዳል። ቂምን እና በቀልን በመተው ለመረዳት፣ ለመተሳሰብ እና ለእርቅ ቦታ እንፈጥራለን።

**3. የውስጥ ሰላም፡-** ይቅርታ የውስጥ ሰላም እና የነፃነት ስሜትን ያመጣል። ያለፈውን ይቅር ብለን እንድላፍ እና በአሁኑ ጊዜ ጥልቅ ግልጽነትን፣ ደስታን እና እርካታን እንድናገኝ ያስችለናል።

**4. የግል እድገት፡-** ይቅርታ የግል እድገትን የሚያቀላጥፍ እና እራስን ማወቅን የሚያጎለብት ታላቅ ተፅዕኖ ያለው እና ዘላለማዊ ለውጥ የሚያመጣ ተግባር ነው። ርኅራኄን፣ መርዳትን እና ከራሳችን ስቃይ በላይ የሌሎችን የህይወት ተሞክሮ የማየት ችሎታን ያስተምረናል።



### 9.1.3 የይቅርታ ሂደት

የይቅርታ ሂደት ለእያንዳንዱ ግለሰብ ልዩ ሲሆን ጊዜ እና ጥረት ሊወስድ ይችላል። በሂደቱ ውስጥ እርስዎን ለመምራት የሚረዱ አንዳንድ ደረጃዎች ከበታች ተጠቅሰዋል፡-

**1. እውቅና መስጠት፡-** እርስዎ ላይ ጉዳት በፈጠረው ሰው ወይም ሁኔታ ምክንያት የተፈጠረውን ህመም ንቁ በመሆን በውስጣችን መኖሩን በማወቅ እውቅና ይስጡ። ከእሱ ወይም ከሁኔታዎቹ ጋር የተያያዙ ስሜቶች ከመደበቅ እና ከመሸሽ ይልቅ እንዲሰማዎት ይፍቀዱ።

**2. ይቅርታን መምረጥ፡-** ይቅር ለማድረግ ንቁ የሆነ ቁርጥ ውሳኔ አድርግ። ይቅር ማለት ያስፈለገው ለራስህ ውስጣዊ ደህንነት እንደሆነ እና የሌሎችን ድርጊት እና ተግባር ችላ ማለት ወይም መርሳት እንዳልሆነ ተረዳ።

**3. ርኅራኄንና መረዳትን መለማመድ፡-** የጎዳዎትን ሰው አመለካከት ለመረዳት ይሞክሩ። እያንዳንዱ ሰው የራሱ የማንነት እና የህይወት ትግል እና ጉድለት እንዳለው በመገንዘብ ለእነሱ ያልዎትን መረዳት እና ርህራሄ በመመርመር ይጨምሩ።

**4. ቂም እና በቀልን መልቀቅ፡-** በውስጥዎ ያለውን የቂም እና የበቀል ፍላጎትን ያስወግዱ። እነዚህን አሉታዊ ስሜቶች አጥብቆ መያዝ እርስዎን እንደሚጎዳ፣ እድገትዎን እንደሚያስተጓጉሉ እና የፈውስ ሂደትን እንደሚያግድ ይረዱ።

**5. ድንበር ማዘጋጀት፡-** ይቅርታ ማለት የሆነውን መርሳት ወይም እንደገና እንድትበደል መፍቀድ ማለት አይደለም። እራስዎን እና ደህንነትዎን ለመጠበቅ ጤናማ ድንበሮችን ያዘጋጁ።

**6. ድጋፍ መፈለግ፡-** ካስፈለገዎት ከታመኑ ጓደኞች፣ የቤተሰብ አባላት ወይም ባለሙያዎች ድጋፍ ይጠይቁ። ስለ ስሜቶችዎ እና ልምዶችዎ ማውራት ጠቃሚ ግንዛቤዎችን እና መመሪያዎችን ሊያገኙ ይችላሉ።

## 9.1.4 ራስን ይቅር ማለት

ሌሎችን ይቅር ከማለት በተጨማሪ ራስን ይቅር ማለትም በተመሳሳይ መልኩ አስፈላጊ ነው። ሁላችንም ስህተቶችን እንሰራለን እናም ላለፉት ድርጊቶች ጥፋተኝነት ወይም እፍረትን እንሸከማለን። ለራስ ርህራሄ እና ይቅርታን በመለማመድ እድገትን እና እራስህን ተቀበል።

**ማጠቃለያ**

ይቅርታ ቁስሎችን የመፈወስ፣ ስሜታዊ ሸክሞችን የማስወገድ እና ውስጣዊ ሰላምን ለማምጣት የሚያስችል ታላቅ ተፅዕኖ ያለው የለውጥ ተግባር ነው። የይቅርታን ጽንሰ ሃሳብ በመረዳት፣ ጥቅሞቹን በማወቅ እና የይቅርታ ሂደትን በመከተል የግል እድገትን፣ የተሻለ ግንኙነትን እና የበለጠ ውስጣዊ ሰላምን ማግኘት እንችላለን። አስታውስ ይቅርታ ለራሳችን የምንሰጠው ስጦታ ሲሆን በርህራሄ፣ በመረዳት እና በቀላል ልብ እንድንራመድ ያስችለናል።



## 9.2 ቁስሎችን መፈወስ እና ስሜታዊ ሸክሞችን መልቀቅ

### መግቢያ

ያለፉ የስሜት ቁስሎችን መፈወስ እና ስሜታዊ ሸክሞችን መልቀቅ በላቀ ውስጣዊ ነፃነት፣ ሰላም እና ስሜታዊ ደህንነት እንድንራመድ የሚያስችለን የለውጥ ሂደት ነው። በዚህ ክፍል ውስጥ የቀድሞ ቁስሎችን ለመፈወስ እና ስሜታዊ ሸክሞችን ለመተው የሚረዱ ቴክኒኮችን እና ልምዶችን እንቃኛለን።

### 9.2.1 ራስን ማጤን እና መቀበል

እራስዎን በማጤን እና የተሸከሙትን ቁስሎች እና የስሜት ሻንጣዎች እውቅና በመስጠት ይጀምሩ። እነዚህ ልምዶች በህይወትዎ እና በደህንነትዎ ላይ ያላቸውን ተፅእኖ ለመረዳት ጊዜ ይውሰዱ።

ቁስሎች እና የስሜት ሻንጣዎች በሁላችንም ዘንድ መኖራቸው የተለመደ መሆኑን በመገንዘብ ራስን መቀበል እና ለራስ ርህራሄን መስጠትን ተለማመዱ። የቀድሞው ልምዶችዎን እንደ ማንነት መገለጫዎ ሳይሆን የጉዞዎ አካል አድርገው በመቀበል እነሱን ለመፈወስ እና ለመልቀቅ ራስን ማጤን እና መቀበልን ይተግብሩ።

### 9.2.2 ስሜቶችን ለመልቀቅ የሚረዱ ዘዴዎች

የታፈኑ ስሜቶችን ለመልቀቅ እና ፈውስን ለማቀላጠፍ የሚረዱ የተለያዩ ዘዴዎች አሉ። ውጤታማ ከሆኑ ዘዴዎች ውስጥ ጥቂቶቹ ከበታች ተገልፆዋል፦

- **ጆርናል መፃፍ፡-** ሃሳብዎን፣ ስሜትዎን እና ልምድዎን በግል መጽሔት ውስጥ ይፃፉ። ይህ ስሜትዎን አስተማማኝ እና ግላዊ በሆነ ስፍራ እንዲገልፁ እንዲሁም በአዲስ እይታ እንዲመለከቱ ያስችልዎታል።

- **ስሜት ለመልቀቅ በሚያስችሉ እንቅስቃሴዎች ውስጥ መሳተፍ፡-** እንደ ዳንስ፣ ዮጋ፣ ወይም በሰውነት ውስጥ የተከማቹ ውጥረቶችን እና ስሜቶችን መልቀቅ በሚያስችሉ አካላዊ እንቅስቃሴዎች ውስጥ ይሳተፉ።

- **የአተነፋፈስ ስራ፡-** ውጥረትን ለመልቀቅ እና የረጋ ስሜትን በውስጥዎ ለመፍጠር የአተነፋፈስ ልምዶችን ይለማመዱ። በአተነፋፈስዎ ላይ በማተኮር፣ እራስዎን ሙሉ በሙሉ ስሜቶቹን እንዲለማመዱ በመፍቀድ እና ስሜቶቹ ከውስጥዎ እንዲለቁ ይፍቀዱ።

### 9.2.3 ይቅርታ እና መተው

በቀድሞ ክፍል ላይ እንደተብራራው ይቅርታ የስሜት ቁስሎችን ለመፈወስ እና የስሜት ሸክሞችን ለመልቀቅ ቁልፍ መሳሪያ ነው። ከራስዎ እና ከሌሎች ጋር የተገናኘ አሉታዊ ገጠመኞች እና ክስተቶች ይቅርታ ማድረግን ተለማመዱ።

መተው እና መልቀቅ መቻል የፈውስ ሂደት አስፈላጊ አካል ነው። ከቀድሞ ቁስሎች ጋር የተያያዙ ህመም፣ ቂም፣ ሀዘን እና አሉታዊ ስሜቶችን ይልቀቁ። እነዚህን ስሜቶች አጥብቆ መያዝ መከራዎን እንደሚያራዝም፣ ስቃይዎን እንደሚጨምር እና እድገትዎን እንደሚያደናቅፍ ይረዱ።

### 9.2.4 ድጋፍ መፈለግ

ያለፈ ቁስሎችን መፈወስ እና የስሜት ሸክሞችን መልቀቅ ፈታኝ ጉዞ ሊሆን ይችላል። ከታመኑ ጓደኞች፣ የቤተሰብ አባላት፣ ወይም እንደ ቴራፒስቶች ወይም አማካሪዎች ካሉ ባለሙያዎች ድጋፍን ይፈልጉ።

መመሪያ እና ድጋፍ ከሚሰጥ ሰው ጋር ስለእርስዎ ልምዶች እና ስሜቶች ማውራት በጣም ጠቃሚ ሊሆን ይችላል። ስሜታዊ ሸክሞችን ለማቅለል እና

ለመልቀቅ ግንዛቤዎችን፣ መሳሪያዎችን እና አስተማማኝ እንዲሁም ምቹ አከባቢ ሊሰጡዎት ይችላሉ።

### 9.2.5 ራስን መንከባከብ እና ራስን መውደድን ማዳበር

አእምሮዎን፣ አካልዎን እና ነፍስዎን በሚመግቡ ራስን የመንከባከብ ልምዶች ውስጥ ይሳተፉ። ደስታን፣ እርካታን እና ውስጣዊ ሰላምን ለሚያመጡልህ ተግባራት ቅድሚያ ስጥ።

እራስህን መውደድን እና ለራስህ ርህራሄ መስጠትን ተለማመድ። የፈውስ ሂደቱን በሚጓዙበት ጊዜ እራስዎን በደግነት፣ መረዳት እና በትዕግስት ይያዙ። በተጨማሪም እራስዎን በአዎንታዊ ተፅእኖዎች በመከበብ ደህንነትዎን በሚያበረታቱ እንቅስቃሴዎች ውስጥ ይሳተፉ።




**ማጠቃለያ**

የቀድሞ ቁስሎችን ለመፈወስ እና የስሜት ሸክሞችን ለመልቀቅ እራስን ማጤንን፣ ስሜት ለመልቀቅ በሚያስችሉ እንቅስቃሴዎች ውስጥ መሳተፍን፣ ይቅርታ ማድረግ እና መተውን፣ ድጋፍን መፈለግን እና ራስን መንከባከብ እና ራስን መውደድን የሚጠይቅ የለውጥ ሂደት ነው። በእነዚህ ልምምዶች ውስጥ በመሳተፍ ካለፉት ቁስሎች ቀስ በቀስ መፈወስ፣ ስሜታዊ ሸክሞችን መልቀቅ እና የበለጠ ነፃነትን፣ ሰላምን እና ስሜታዊ ደህንነትን ማግኘት ይችላሉ። ያስታውሱ ፈውስ ጊዜ እና ጥረት የሚጠይቅ መንፈሳዊ ጉዞ ነው። በዚህ የለውጥ ጎዳና ላይ ስትጓዙ ታጋሽ እና ገር ሁን።

## 9.3 ይቅርታን ለማዳበር እና ውስጣዊ ሰላምን ለመፍጠር የሚረዱ ልምዶች

### መግቢያ

ለራሳችንም ሆነ ለሌሎች የይቅርታ ልምድን ማዳበር እና የውስጥ ሰላምን መፍጠር ለስሜታዊ ደህንነት እና ለግል እድገታችን አስፈላጊ ናቸው። በዚህ ክፍል ውስጥ ይቅርታን ለማዳበር እና በህይወትዎ ውስጥ ውስጣዊ ሰላም ለመፍጠር የሚረዱዎትን ልምዶችን እንመረምራለን።

### 9.3.1 የማስተዋል ተመስጦ

የማስተዋል ተመስጦ ይቅርታን ለማዳበር እና ውስጣዊ ሰላም ለመፍጠር የሚረዳ ታላቅ ተፅዕኖ ያለው ልምምድ ነው። ትኩረትዎን አሁን ወዳለው ጊዜ በማምጣት እና ሃሳቦችዎን እና ስሜቶችዎን ያለፍርድ በመመልከት የበለጠ የእራስን ግንዛቤ እና ርህራሄ ስሜትን ማዳበር ይችላሉ።

በተመስጦ ጊዜ ለራስህ እና ለሌሎች ይቅርታ በመስጠት እና ልምድህን በማዳበር ላይ አተኩር። ከቀድሞ ጉዳቶች ጋር የተዛመዱ አሉታዊ ሀሳቦችን እና ስሜቶችን ከራስዎ ሲወጡ በአይነ ህሊናዎ በመመልከት መተውን በተደጋጋሚ ይለማመዱ። የአሁኑን ጊዜ ያለ አሉታዊ ሀሳብ እና ስሜት በመቀበል በእራስዎ ውስጥ የሰላም ስሜት በመፍጠር ቀስበቀስ ያዳብሩ።

### 9.3.2 የፍቅራዊ ደግነት ተመስጦ

ፍቅራዊ ደግነት ተመስጦ እንዲሁም ሜታ ሜዲቴሽን በመባል የሚታወቅ ሲሆን ፍቅር እና ርህራሄ የተሞላባቸው ሃሳቦችን እና ስሜቶችን ለራሳችን እና ለሌሎች መላክን የሚያካትት ልምምድ ነው። ይህ ልማድ ይቅር ባይነትን፣ መረዳትን፣ ርኅራኄን እና ውስጣዊ ሰላምን ለማዳበር ይረዳል።

በተመስጦ ወቅት ፍቅራዊ ደግነትን ንቁ በሆነ ህሊና ወደ ራስህ በመምራት ጀምር። እንደ "ደስተኛ ልሁን፣ ሰላም ልሁን፣ ከስቃይ ነፃ ልውጣ" ያሉ ሀረጎችን ከመጠቀም ይልቅ ''ደስተኛ ነኝ፣ ሰላም ነኝ፣ በፀጋ የተከበብኩ ነኝ ያሉ ሀረጎችን በመድገም እና ደስተኛ፣ ሰላማዊ እና እርካታ የተሙሉበትን የቀድሞ የህይወት ልምምዶች ወይም ትውስታዎች መልሰን በአይነ ህሊናችን በመመልከት ተመሳሳይ የሆነ ውስጣዊ ሁኔታ መፍጠር እንችላለን። ከዚያም እነዚህን ምኞቶች የጎዱዎትን፣ ያስቀየመዎትን፣ ያስከፋዎትን ጨምሮ ይህን አዎንታዊ ሁኔታ በስጦታ መልክ ያቅርቡ። በውስጥዎ ፍቅራዊ ደግነትን በማዳበር ልብዎን ማለስለስ እና ውስጣዊ ሰላም መፍጠር ይችላሉ።

### 9.3.3 የምስጋና ልምምድ

ምስጋና ትኩረትዎን ከአሉታዊነት ወደ አዎንታዊነት ሊያሸጋግር የሚችል ልምምድ ነው። ምስጋናን ማዳበር ላሁኑ ጊዜ ያለንን ቅሬታ ለማስወገድ እና ውስጣዊ ሰላምን ለመፍጠር ይረዳዎታል።

አመስጋኝ በሚሆኑባቸው ነገሮች ላይ ለማሰላሰል በየቀኑ ጊዜ ይውሰዱ። በምስጋና ጆርናል ውስጥ ይፃፏቸው ወይም ዝም ብለው በአእምሮዎ ውስጥ ምስጋናዎን ይግለጹ። በህይወትዎ አወንታዊ ገጽታዎች ላይ በማተኮር ይቅርታን ማዳበር እና ውስጣዊ ሰላምን መፍጠር ይችላሉ።

### 9.3.4 ራስን ማፍቀር

ይቅርታን ለማዳበር እና ውስጣዊ ሰላምን ለመፍጠር ራስን ማፍቀር እና ርህራሄን መስጠት መቻል አስፈላጊ ነው። በተለይ ስህተት ስትሠራ ወይም ፈተናዎችን ስትጋፈጥ እራስህን በደግነት፣ በማስተዋል እና በተቀባይ እጅ መያዝ ተገቢ ነው።

ህመምህን እና ስቃይህን በመቀበል እና ለራስህ የማጽናኛ እና የድጋፍ ቃላትን በመስጠት ለራስህ ርህራሄ እና ፍቅር መስጠትን ተለማመድ። በአስቸጋሪ እና በፈተና ጊዜ ውድ ጓደኛህን እንደምትደግፍ እና እንደምትይዝ ሁሉ እራስህንም

በተመሳሳይ መልኩ ያዝ ከሌሎች አጠብቅ። ለራስ ርኅራኄ እና ፍቅርን በማዳበር ያለፉ ቁስሎችን መፈወስ እና ውስጣዊ ሰላም መፍጠር ይችላሉ።

## 9.3.5 ማስተዋል የተሞላበት ግንኙነት

ይቅርታን ለማዳበር እና በግንኙነቶች ውስጥ ውስጣዊ ሰላም ለመፍጠር ውጤታማ እና ማስተዋል ያለው ግንኙነት መፍጠር አስፈላጊ ነው። በትኩረት በማዳመጥ፣ በደግነት እና ርህራሄ በመናገር እና ፍላጎቶችዎን እና ስሜቶችዎን በሰላማዊ መንገድ በመግለጽ ማስተዋል የተሞላበት ግንኙነትን ይለማመዱ።

ግጭቶች በሚፈጠሩበት ጊዜ ለመረዳት እና የጋራ መግባባትን ለማግኘት በክፍት አእምሮ እና በፈቃደኝነት ይቅረቡ። ሁል ጊዜ ትክክለኛ የመሆንን ፍላጎት በመተው መፍትሄ ለማግኘት እና ስምምነትን በመፍጠር ላይ በማተኮር ይቅርታን ማድረግን ይለማመዱ።



**ማጠቃለያ**

ይቅርታን ማዳበር እና ውስጣዊ ሰላምን መፍጠር ማስተዋልን፣ ለራስ ርህራሄ መስጠትን፣ ምስጋናን መለማመድን እና ማስተዋል የተሞላበት ግንኙነትን መፍጠር የሚሹ የለውጥ ልምምዶች ናቸው። በእነዚህ ልምምዶች ውስጥ በመሳተፍ ቂምን መልቀቅ፣ ያለፉትን ቁስሎች መፈወስ እና በህይወታችሁ ውስጥ ውስጣዊ ሰላም መፍጠር ትችላላችሁ። አስታውስ ይቅርታን መለማመድ እና ውስጣዊ ሰላምን መፍጠር ትዕግስትን፣ ራስን ማጤን እና ቁርጠኝነትን የሚጠይቁ ቀጣይነት ያላቸው ተግባራት ናቸው። እነዚህን ልምዶች በመቀበል የበለጠ ሰላማዊ እና አርኪ ህይወት እንዲኖርዎት ይፍቀዱላቸው።

# ምዕራፍ 10፡ የፍቅር እና የርህራሄ ህግ

## 10.1 ፍቅርን እና ርህራሄን እንደ ከፍተኛ የንዝረት ጉልበት መቀበል

**መግቢያ**

ፍቅር እና ርህራሄ ህይወታችንን እና በዙሪያችን ያለውን አለም ሊለውጡ የሚችሉ ታላቅ ተፅዕኖ ያላቸው ሀይሎች ናቸው። በዚህ ምእራፍ ውስጥ የፍቅር እና የርህራሄን ጽንሰ-ሀሳብ እንደ ከፍተኛ ንዝረት ጉልበት ስለመሆናቸው እና እነሱን ማቀፍ እንዴት አወንታዊ ለውጥ እና እርካታ እንደሚያመጣ እንመረምራለን።

### 10.1.1 ፍቅርን እና ርህራሄን መረዳት

ፍቅር እና ርህራሄ እርስበርስ የተሳሰሩ እና ስር የሰደዱ የሰው ልጆች መሰረት ናቸው። ፍቅር ከራሳችን፣ ከሌሎች እና ከአለም ጋር ጥልቅ የሆነ የመዋደድ፣ የመተሳሰብ እና የመተሳሰር ስሜት ነው። ርኅራኄ የሌሎችን ስቃይ እና ፈተና የመረዳት ችሎታ እና እሱን የማቃለል ፍላጎት እና ተግባር ነው።

ፍቅርን እና ርህራሄን ስንቀበል ወደ ከፍተኛው የማንነታችን ንዝረት እንገባለን። እነዚህ ንዝረቶች አወንታዊ ጉልበትን፣ ደግነትን እና መረዳትን በማሰራጨት እራሳችንን እና በዙሪያችን ያሉትን ሰዎች ከፍ ሊያደርግ እና ሊለውጥ የሚችል የሞገድ ተፅዕኖ ይፈጥራል።

### 10.1.2 ራስን መውደድን ማዳበር

ራስን መውደድ መቻል ፍቅርን እና ርህራሄን ለመቀበል መሰረት ነው። ራስን መውደድ እራሳችንን መቀበል እና መንከባከብን፣ ብቁ መሆናችንን ማወቅ እና እራሳችንን በደግነትና በጥንቃቄ መያዝን ያካትታል።

ራስን በመንከባከብ ተግባራት ውስጥ በመሳተፍ፣ ጤናማ ድንበሮችን በማውጣት እና ከራስህ ጋር በደግነት እና አዎንታዊ በሆነ መንገድ በመናገር ራስን መውደድን ተለማመድ። እንደማንኛው ፍጥረት ፍቅር እና ርህራሄ የሚገባዎት መሆንዎን በማወቅ ጥንካሬዎን እና ጉድለቶችዎን ይቀበሉ።

### 10.1.3 ፍቅራዊ ደግነትን መለማመድ

ፍቅራዊ ደግነት ለራሳችን እና ለሌሎች ፍቅርን እና መልካም ምኞቶችን መስጠትን የሚያካትት ልምምድ ነው። ፍቅራዊ ደግነትን በማዳበር የፍቅርና የርኅራኄ ንዝረታችንን ማስፋት እንችላለን።

ፍቅራዊ ደግነትን ወደ ራስህ በመምራት ጀምር። እንደ "ደስተኛ ነኝ፣ ጤናማ ነኝ፣ ደህና ነኝ፣" የሚሉ ሀረጎችን ለራስህ በመድገም እና በመጠቀም እነዚህን ምኞቶች ለሌሎችም ጭምር ያቅርቡ። ፍቅራዊ ደግነትን በመለማመድ በራስህ ውስጥ ጥልቅ የሆነ የፍቅር እና የርህራሄ ስሜት ማዳበር ትችላለህ።

### 10.1.4 የደግነት ተግባራት እና የአገልግሎት ውስጥ መሳተፍ

ፍቅር እና ርህራሄን መቀበል እርምጃ መውሰድ እና በአለም ላይ በጎ ተጽእኖ መፍጠርን ያካትታል። በበጎ ፈቃደኝነት በመሳተፍ፣ በችግር ላይ ያለ ጓደኛን በመርዳት ወይም በቀላሉ ሰሚ ጆሮ በመስጠት በውስጥዎ ያለውን የፍቅር እና የርህራሄ ስሜት ያጎልብቱ።

ትናንሽ የደግነት ተግባራት በሰጪውም ሆነ በተቀባዩ ላይ ከፍተኛ ተጽዕኖ ሊያሳድሩ የሚችሉ ሲሆን ይህም በዙርያችን የፍቅር እና የርህራሄ ሞገድ ይፈጥራል። በመጨረሻም በዕለት ተዕለት ሕይወትዎ ውስጥ ፍቅርን እና ርህራሄን ለማስፋፋት እና በሌሎች ህይወት ላይ ለውጥ ለማምጣት እድሎችን ይፈልጉ።

### 10.1.5 ርህራሄን እና መረዳትን ማዳበር

ርህራሄ የሌሎችን ስሜት የመረዳት እና የመጋራት ችሎታ ነው። ርኅራኄን ማዳበር ከሌሎች ጋር በጥልቀት እንድንገናኝ እና በርኅራኄ ምላሽ እንድንሰጥ ያስችለናል።

ንቁ ማዳመጥን በመለማመድ የሌሎችን አመለካከቶች እና ልምዶች ለመጋራት እና ለመረዳት ጣሩ። እራስህን በነሱ ሁኔታ ውስጥ በማስገባት ምን ሊሰማቸው እንደሚችል አስብ። ርህራሄን እና መረዳትን በማዳበር በግንኙነቶችዎ እና በመስተጋብርዎ ውስጥ ፍቅር እና ርህራሄን ማጎልበት ይችላሉ።

**ማጠቃለያ**

ፍቅርን እና ርህራሄን እንደ ከፍተኛ ንዝረት ጉልበት መቀበል አወንታዊ ለውጥን እና እርካታን ሊያመጣ የሚችል ልምምድ ነው። ራስን መውደድን በማዳበር፣ ፍቅራዊ ደግነትን በመለማመድ፣ በደግነት ተግባራት እና በአገልግሎት ውስጥ በመሳተፍ፣ እና ርኅራኄን እና መረዳትን በማዳበር በህይወትዎ እና በዙሪያዎ ወዳለው ዓለም  ፍቅር እና ርህራሄን ማሰራጨት ይችላሉ። እነዚህን ልምምዶች በመቀበል ይበልጥ ወደ ተገናኘ፣ ርህራሄ የተሞላበት እና አርኪ ወደሆነ ህይወት እንዲመራዎት ይፍቀዱ።

## 10.2 ራስን መውደድን ማዳበር እና ለሌሎች ማካፈል

### መግቢያ

ራስን መውደድን ማዳበር ለደህንነታችን እና ለግል እድገታችን አስፈላጊ ነው። ራሳችንን ስንወድ ያንን ፍቅር ለሌሎች ለማካፈል እና ለማዳረስ ምቹ ሁኔታ እንፈጥራለን። በዚህ ክፍል ውስጥ እራስን መውደድን ለማዳበር የሚረዱ ልምዶችን እና በዙሪያችን ላሉ ሰዎች የምናጋራበትን መንገዶች እንቃኛለን።

### 10.2.1 ራስን መውደድን መረዳት

ራስን መውደድ ለጤናማ ግንኙነት እና አርኪ ህይወት መሰረት ነው። እራሳችንን እንደ ራሳችን መቀበልን፣ ብቁ መሆናችንን ማወቅ እና እራሳችንን በደግነት፣ በርህራሄ እና በአክብሮት መያዝን ያካትታል።

ራስን መውደድን ለማዳበር ጥንካሬዎን፣ ጉድለቶችዎን በመቀበል እና ራስን መንከባከብን በመለማመድ ይጀምሩ። ለምትወደው ጓደኛ በምታቀርበው ተመሳሳይ ፍቅር እና ርህራሄ እራስህን ያዝ።

### 10.2.2 ለራስ ርህራሄ መስጠትን መለማመድ

ለራስ ርህራሄን መስጠት ራስን የመውደድ ዋና አካል ነው። የራሳችንን ህመምና ፈተና አምነን በደግነትና በማስተዋል ምላሽ መስጠትን ይጨምራል።

ተግዳሮቶች ወይም ስህተቶች ሲያጋጥሙህ ለራስህ የማጽናኛ እና የድጋፍ ቃላትን በመስጠት ለራስህ ርህራሄን መስጠትን ተለማመድ። ለምትወደው ሰው በምታቀርበው ተመሳሳይ ርህራሄ እራስህን ያዝ። ሰብአዊነትዎን በመቀበል ስህተት መስራት የእድገት እና የመማር አካል መሆኑን ይወቁ።

## 10.2.3 ጤናማ ድንበሮችን ማዘጋጀት

ጤናማ ድንበሮችን ማዘጋጀት ራስን የመውደድ ተግባር ነው። የራስዎን ፍላጎቶች፣ እሴቶች እና ገደቦች ማወቅ እና ማክበርን ያካትታል።

ፍላጎቶችዎን በግልፅ በማስተላለፍ እና አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ እራስዎን በማረጋገጥ ድንበሮችን ማዘጋጀት ይለማመዱ። ያለጥፋተኝነት ወይም ሌሎችን የማሳዘን ፍርሃትን እምቢ ማለትን ተማር። ጤናማ ድንበሮችን በማዘጋጀት ደህንነትዎን ይጠብቃሉ እንዲሁም ራስን የመውደድ ስሜቶች እንዲያብብ ምቹ ቦታ ይፈጥራሉ።

## 10.2.4 ምስጋናን እና ራስን ማድነቅን መለማመድ

ምስጋና እና ራስን ማድነቅ ራስን መውደድን ማዳበር የሚያስችሉ ልምዶች ናቸው። ለራስዎ እና በህይወትዎ ውስጥ ላሉ የሚያደንቋቸው ነገሮች ለማሰላሰል በየቀኑ ጊዜ ይውሰዱ።

በራስህ ማንነት ውስጥ የምታደንቃቸውን ጥንካሬዎችህን፣ ስኬቶችህን እና ባህሪዎችህን ጻፍ ወይም በአእምሮ እውቅና ስጥ። የእርስዎን ማንነት ልዩ ለሚያደርጉ ልዩ ባህሪያት እና ልምዶች ምስጋናን ይስጡ። ምስጋናን እና እራስን ማድነቅን በመለማመድ እራስን የመውደድ ስሜትን ያጠናክራሉ እንዲሁም አዎንታዊ የራስ ምስልን ያዳብራሉ።

## 10.2.5 ለሌሎች ፍቅርን እና ደግነትን ማስፋት

አንዴ እራስን መውደድን ካዳበርክ ለሌሎች ማስፋት ትችላለህ። እራስህን ስትወድ የበለጠ የምትሰጠው ፍቅር ይኖርሃል።

ርህራሄን፣ መልካምነትን እና መረዳትን በማሳየት ለሌሎች ፍቅርን እና ደግነትን ተለማመዱ። በትኩረት ያዳምጡ፣ ድጋፍ ይስጡ እና የደግነት ድርጊቶችን ይከውኑ። ለሌሎች ፍቅርን በማራዘም አወንታዊ የሞገድ ውጤት በመፍጠር የበለጠ አፍቃሪ እና ሩህሩህ ዓለም እንዲፈጠር አስተዋፅዖ ያደርጋሉ።

**ማጠቃለያ**

እራስን መውደድን ማዳበር በእውነተኛነት እንድንኖር እና እርካታ የሞላቸው ግንኙነቶችን እንድንፈጥር የሚያስችል ተግባር ነው። ለራስ ርኅራኄ መስጠትን በመለማመድ፣ ጤናማ ድንበሮችን በማዘጋጀት፣ ምስጋና እና ራስን ማድነቅን በመለማመድ፣ ለሌሎች ፍቅር እና ደግነት በመስጠት፣ እራስን መውደድን ማዳበር እና በአለም ላይ አዎንታዊ ተጽእኖ መፍጠር ይችላሉ። እነዚህን ልምዶች በመቀበል እና ራስን በመውደድ ፍቅር፣ ርህራሄ እና እርካታ የተሞላ ህይወት እንዲመራዎት ይፍቀዱ።

## 10.3 ፍቅር እና ርህራሄ እንዴት ግንኙነቶችዎን እና አለምን መለወጥ ይችላሉ

**መግቢያ**

ፍቅር እና ርህራሄ ግለሰባዊ ህይወትን ብቻ ሳይሆን ግንኙነታችንን እና አለምን የመለወጥ ሃይል አላቸው። በዚህ ክፍል ውስጥ ፍቅር እና ርህራሄ እንዴት አወንታዊ ለውጥ እንደሚያመጡ እና የበለጠ እርስበርስ ተስማምቶ መኖር የሚችል እና ሩህሩህ አለም መፍጠር እንደሚችሉ እንመረምራለን።

### 10.3.1 ጠንካራ እና ጤናማ ግንኙነት መፍጠር

ፍቅር እና ርህራሄ የጠንካራ እና ጤናማ ግንኙነቶች የማዕዘን ድንጋይ ናቸው። ግንኙነታችንን በፍቅር እና በርህራሄ ስንቃረብ ለእድገት፣ ለግንዛቤ እና ለግንኙነት አስተማማኝ፣ ምቹ እና ተንከባካቢ ቦታ እንፈጥራለን።

በግንኙነቶችዎ ውስጥ በማስተዋል ማዳመጥን፣ መተሳሰብን እና መረዳትን ተለማመዱ። እንዲሁም ለምትወዳቸው ሰዎች አድናቆትን፣ ደግነትን እና ድጋፍን ያሳዩ። በግንኙነትዎ ውስጥ ፍቅርን እና ርህራሄን በማዳበር መተማመንን ያሳድጋሉ፣ ግንኙነቶችን ያጠናክራሉ፣ እና ለረጅም ጊዜ የሚቆይ እና ጠንካራ ትስስር ለመፍጠር መሰረት ይጥላሉ።

### 10.3.2 ግጭቶችን በፍቅር እና ርህራሄ መፍታት

ግጭቶች የማንኛውም ግንኙነት ተፈጥሯዊ አካል ናቸው። ነገር ግን ፍቅር እና ርህራሄ ገንቢ እና ሰላማዊ በሆነ መንገድ እንድንፈታ ይረዱናል። አለመግባባቶችን በቁጣ ወይም በጉልበት ምላሽ ከመስጠት ይልቅ በፍቅር እና በርህራሄ መፍትሄ ለማግኘት ይጣሩ።

የሌላውን ሰው አመለካከት እና ስሜት ለመረዳት በመሞከር ርህራሄን ይለማመዱ። በግልጽ እና በሐቀኝነት በመናገር፣ ፍላጎቶችዎን እና ስጋቶችዎን በመግለጽ እንዲሁም የሌላውን ሰው አስተያየት ማዳመጥ ተገቢ ነው። መግባባትን፣ ስምምነትን እና የጋራ እድገትን ቅድሚያ የሚሰጡ መፍትሄዎችን ይፈልጉ። ግጭቶችን በፍቅር እና በርህራሄ በመፍታት ግንኙነቶችን ማጠናከር፣ ጥልቅ ግንዛቤን እና ግንኙነትን ማጎልበት ይችላሉ።



### 10.3.3 ፍቅርን እና ርህራሄን በአለም ውስጥ ማስፋፋት

እኛ የምንፈጥረው ፍቅር እና ርህራሄ ከቅርብ ግንኙነቶቻችን በላይ የሚዘልቅ ተዘዋዋሪ ተፅእኖን የመፍጠር ሃይል አላቸው። ፍቅር እና ርህራሄን በድርጊታችን እና በግንኙነታችን ውስጥ በማካተት የበለጠ ሩህሩህ እና ስምምነት ያለው ዓለም ለመፍጠር አስተዋጽዖ ማድረግ እንችላለን።

በጎ ፈቃደኝነት፣ የበጎ አድራጎት እንቅስቃሴዎችን መደገፍ፣ ወይም በቀላሉ ለተቸገሩት የእርዳታ እጅ በመስጠት በደግነት አገልግሎት ውስጥ ይሳተፉ። ከተለያዩ አስተዳደግ እና ባህሎች ለመጡ ሰዎች መተሳሰብ እና መረዳትን ተለማመዱ። ፍቅር እና ርህራሄን በአለም ውስጥ በማስፋፋት ሌሎች ተመሳሳይ ነገር እንዲያደርጉ ማነሳሳት እና በትልቅ ደረጃ አዎንታዊ ተጽእኖ መፍጠር እንችላለን።

## 10.3.4 ፍቅርን እና ርህራሄን በህብረተሰብ ውስጥ ማዳበር

ፍቅር እና ርህራሄ ማህበረሰቡን በአጠቃላይ መለወጥ ይችላል። ለማህበራዊ ፍትህ፣ እኩልነት፣ እና ሁሉ አቀፍነትን በመደገፍ የበለጠ ሩህሩህ እና ፍትሃዊ ማህበረሰብ መፍጠር እንችላለን።

ፍቅርን፣ ርህራሄን እና ማህበራዊ ለውጥን የሚያበረታቱ መንስኤዎችን ይደግፉ። እራስዎንም ሆነ ሌሎችን ስለ ፍቅር፣ ርህራሄ፣ መተሳሰብ፣ መረዳት እና የደግነት አስፈላጊነትን ያስተምሩ። የበለጠ ሩህሩህ ማህበረሰብ ለመፍጠር ንቁ በመሆን እና በማስተዋል በመሳተፍ ፍቅር እና ርህራሄ በሁሉም ዘንድ ዋጋ እንዲኖረው የጋራ አስተዋፅዖ ማድረግ እንችላለን።

**ማጠቃለያ**

ፍቅር እና ርህራሄ ግንኙነታችንን እና አለምን የመቀየር ሀይል አላቸው። ጠንካራ እና ጤናማ ግንኙነቶችን በመገንባት፣ ግጭቶችን በፍቅር እና በርህራሄ በመፍታት፣ ፍቅርን እና ደግነትን በአለም ውስጥ በማስፋፋት እና ፍቅር እና ርህራሄን በህብረተሰብ ውስጥ በማጎልበት የበለጠ እርስበርስ የሚስማማ፣ የተሳሰረ፣ የተገናኘ እና ርህራሄ ያለው ዓለም መፍጠር እንችላለን። ፍቅርን እና ርህራሄን በህይወትዎ ውስጥ እንደ መሪ መርሆች በመቀበል በግንኙነቶችዎ እና በዙሪያዎ ባለው አለም አወንታዊ ለውጥ ማምጣት ይችላሉ።

## ማጠቃለያ

"የሰማይ ህጎች፡ በስምምነት የመኖር ሚስጥር" የእኛን እውነታ ስለሚቆጣጠሩ መሰረታዊ ህጎች አጠቃላይ ግንዛቤ ሰቷል። ከእነዚህ ህጎች ጋር እራሳችንን በማጣጣም የተትረፈረፈ፣ የተሟላ እና የደስታ ህይወት የመፍጠር ሃይል አሎት። ያስታውሱ እርስዎ የእውነትዎ ተባባሪ ፈጣሪ ነዎት። መንፈሳዊ አለምም ሁል ጊዜ ለእርስዎ ሞገስ እየሰራ ነው። እነዚህን ህጎች ተቀበል፣ በየቀኑ ተለማመዳቸው እና ህይወትህ በተአምራዊ መንገድ ሲለወጥ ተመልከት። ጉዞዎም በፍቅር፣ በብርሃን እና ማለቂያ በሌለው እድሎች የተሞላ ይሁን።



# ያገኘህውን

# ትምህርት




# እንጂ

# ስህተቴን

# አትቁጠር።



ኤጻጉሜን
(ኔቶ)

እንኳን ወደ "የሰማይ ህጎች፡ በስምምነት የመኖር ሚስጥር" በደህና መጡ። በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ከራሳችንም ሆነ ከፍጥረት አለም ጋር በስምምነት ለመኖር የሚረዱ መሰረታዊ መርሆችን እና ከነዚህ መርሆዎች ጋር አብረን በስምምነት መኖር እንዴት ማንነታችንንም ሆነ ህይወታችንን መለወጥ እንደሚችል እንመረምራለን። ወደ ዩኒቨርስ ጥበብ ዘልቀን በመግባት የተትረፈረፈ፣ የተሟላ እና የደስታ ህይወት ለመፍጠር የሚረዱ ግንዛቤዎችን እና መሳሪያዎችን ያገኛሉ። የእኛን እውነታ የሚቀርጹ መርሆዎች በምንመረምርበት ጊዜ ራስዎን የበለጠ ለማወቅ፣ ከራስዎ በስምምነት ለመኖር እና ወደ ተሻለ የማንነት እና የህይወት ደረጃ የማብቃት ጉዞ ለመጀመር ይዘጋጁ።